# የጅብሪል ሐዲስ ማብራሪያ

በሸይኽ ሷሊህ ፈውዛን አል ፈወዛን




ቅንብር

ዶ/ር ዓዲል ቢን ሙሀመድ

ትርጉም

ዩሱፍ አህመድ ወንድማገኝ

በኢብኑ መስዑድ ኢስላሚክ ሴንተር
የመፃህፍት ትርጉምና ዝግጅት ክፍል የተገመገመ

# የጅብሪል ሐዲስ ማብራሪያ


በዶ/ር ሷሊህ ብን ፈውዛን አልፈውዛን

ዝግጅት
ዶ/ር ዓዲል ብን ሙሀመድ

ትርጉም
ዩሱፍ አህመድ ወንድማገኝ

# ማውጫ

# የአርታኢው መቅድም

የዚህ መፅሀፍ መሰረት **የሸይኽ ሳሊህ ፈውዛን አልፈውዛን “ሸርሁ ሀዲሲ ጂብሪል”** በሚል ርዕሥ መድረክ ላይ ያስተላለፉት ትምህርት ነው:: **በዶ/ር ዓዲል ሙሀመድ** በፅሁፍ ተቀናብሮ በአረብኛ ቋንቋ የተዘጋጀ ሲሆን በወንድም **ዩሡፍ አህመድ** በአገራችን በሠፊው በሚነገረው አማራኛ ቋንቋ ተተርጉሞ ቀርቦልናል::

**የኢብኑ መስዑድ ኢስላሚክ ሴንተር የመፃህፍት ትርጉምና ዝግጅት ክፍል** ይህንን ትርጉም ገምግሞ አስፈላጊውን እርማት ያደረገ ሲሆን ሠፊውን የሙስሊም ማህበረሰብ እንደሚጠቅም አምኖበታል::

አላህ ተናጋሪውን አዘጋጁንና ተርጓሚውን ላበረከቱት መልካም ስራ በዕጥፍ ድርብ እንዲመነዳቸው እንለምነዋለን::

## የማዕከሉ አድራሻ

☏ +251112781893
Fax: +251112779660
e-mail:-info@nesiha.org
www.nesiha.org
አዲስ አበባ
ኢትዮጵያ

# የተርጓሚው ማስታወሻ

ይህ፤ ዶክተር ሷሊህ ቢን ፈውዛን ቢን አብደላህ አልፈውዛን አል-አርበኢን አነወዊያህ ለተባለው መጽሀፍ ከሰጡት የድምጽ ማብራርያ የጅብሪልን ሀዲስ የተመለከተዉን ክፍል ዶክተር ዓዲል ብን ሙሀመድ ወደ መፅሀፍ በመቀየር «ሸርህ ሀዲሱ ጅብሪል» (የጅብሪ ልሀዲስ ማብራሪያ) በሚል ርዕስ ያቀረቡት መፅሀፍ ነው::

ይህን መፅሀፍ ለመተርጎም ያነሳሳኝ መፅሀፉ በዲነል ኢስላም ውስጥ እጅግ መሰረታዊ የሆኑ ቁም ነገሮችን መያዙ ሲሆን በአማርኛ ቋንቋ ቢቀርብ ለሀገራችን ሙስሊም ህብረተሰብ ያለውን ጠቀሜታ በማሰብ ነው:: በትርጉሙ ሂደት ነፃ የአተረጓጎም ስልትን ተከትያለሁ፣ አንባቢያን መፅሀፉን በጥሩ መልኩ መረዳት ይችሉ ዘንድ ድግግሞሽ ያለባቸው አገላለፆችና ሀሳቦች አጥረው እንዲቀርቡ ወይም እንዲቀነሱ፣ በአረፍተ ነገሮች አደረጃጀት ላይም እንደዚሁ አስፈላጊ የሆኑ መጠነኛ ለውጦችን አድርጊያለሁ::

በመፅሀፉ አተረጓጎም እና ይዘት ላይ አስተያየት ወይም እርምት ካላችሁ፤ በስልክ ቁጥር 0918 760 831/0920 762 881 ደዉላችሁ ብትነግሩኝ ወይም በፖስታ ሳጥን ቁጥር 1431 (ባህር ዳር) ብትልኩልኝ በደስታ እቀበላለሁ::

አላህ ይህንን መጽሀፍ ለመላው ሙስሊም ማህበረሰብ የሚጠቅም ያደርገው ዘንድ እለምነዋለሁ::

ተርጓሚው
ዩሱፍ አህመድ ወንድምአገኝ

# መግቢያ

ምስጋና ለአለማት ጌታ ለአላህ የተገባ ነው። የአላህ ሰላምና እዝነት በነብዩ ﷺ ፣ በቤተሰቦቻቸውና በጓደኞቻቸው ላይ ሁሉ ይስፈን።

ይህን መፅሀፍ ያዘጋጀሁት ዶክተር ሷሊህ ብን ፈውዛን ብን አብደላህ አልፈውዛን አርበኢን ሀዲስን ሲያስተምሩ ለሀዲሱ ጅብሪል የሰጡትን ማብራሪያ ወደ መፅሀፍ በመቀየር ነው። አላህ ለእርሳቸው፣ ለወላጆቻቸውና በአጠቃላይ ለሙስሊሙ ህብረተሰብ ምህረት እንዲያደርግ እለምናለሁ።

ሀዲሱ ጅብሪል፣ ከሀዲሶች ሁሉ ትልቅ ደረጃ የሚሰጠው ሲሆን፣ በቁርአን ውስጥ የፋቲሃ (የመክፈቻው ምዕራፍ) «የቁርዓን እናት» ተብሎ እንደሚጠራ ሁሉ፤ይህም ሀዲስ በታላላቅ አሊሞች ዘንድ «ኡሙ ሱና» ወይም «የሀዲሶች ሁሉ እናት» በመባል ይጠራል። «የሀዲሶች ሁሉ እናት» ለመባል የበቃውም ሀዲሶች ሁሉ የሚሽከረከሩት ይህ ሀዲስ በያዘው መሰረታዊ ሀሳብ ዙሪያ በመሆኑ ነው።

ሀዲሱ በዋናነት ስድስቱን የእምነት እና አምስቱን የኢስላም መሰረቶች እንዲሁም ኢህሳንን (ከአላህ ጋር ሊኖር የሚገባውን ፍፁማዊ ግንኙነት) እና የቂያማ (የትንሳኤ) ምልክቶችን በውል ይዘክራል።

በመጨረሻም አላህ ሸይኻችን ዶክተር ሷሊህ ብን ፈውዛንን ወደ ቅን መንገድ ተጣሪና እንዲያደርጋቸው፣ እርሳቸውንም ሆነ ቤተሰቦቻቸውን በአላህ የእዝነት ጥላ ስር ከሚውሉ ሰዎች ያደርጋቸው ዘንድ እለምነዋለሁ።

ዶክተር አዲል ብን ሙሀመድ

# ሀዲሱ ጅብሪል

ምስጋና ለአለማት ጌታ የተገባ ነው:: የአላህ እዝነት በነብዩ፣ በቤተሰቦቻቸውና በባልደረቦቻቸው እንዲሁም እስከ ትንሳኤ ድረስ ቅኑን ጎዳና በተከተሉት ላይ ሁሉ ይውረድ:: ከኡመር ኢብኑ አልኸጧብ ﵁[1] የተላለፈውና **የሀዲሶች ሁሉ እናት** የተሰኘው ይህ ሀዲስ የሚከተለው ነው:-

***አንድ ቀን ከነብዩ ጋር ተቀምጠን እያለ፤ ልብሱ በጣም ነጭ፣ ፀጉሩ በጣም ጥቁር የሆነ ግለሰብ ብቅ አለ:: ግለሰቡን ከዚህ በፊት የሚያውቀው ሰው አልነበረም:: በሌላ በኩል አንድም መንገደኛ መሆኑን የሚጠቁም ምልክት አይታይበትም:: ጉልበቶቹን ወደ ነብዩ ጉልበቶች በማስጠጋትና እጆቹን ጭኖቹ ላይ አድርጎ፣ ከነብዩ ፊት-ለፊት ተቀመጠ:: ከዚያም የሚከተሉትን ጥያቄዎች አቀረበ:-***

قال يا محمد أخبرني عن الإسلام فقال رسول الله صلى الله عليه وآله وسلم: الإسلام أن تشهد أن لا إله إلا الله وأن محمدا رسول الله وتقيم الصلاة وتؤتي الزكاة وتصوم رمضان وتحج البيت إن استطعت إليه سبيلا قال: صدقت فعجبنا له يسأله ويصدقه قال: فأخبرني عن الإيمان قال أن تؤمن بالله وملائكته وكتبه ورسله واليوم الآخر وتؤمن بالقدر خيره وشره قال: صدقت قال: فأخبرني عن الإحسان قال أن تعبد الله كأنك تراه فإن لم تكن تراه فإنه يراك قال: فأخبرني عن الساعة قال ما المسئول عنها بأعلم من السائل قال: فأخبرني عن أماراتها قال أن تلد الأمة ربتها وأن ترى الحفاة العراة العالة رعاء الشاء

[1] ይህ የአረብኛ ቃል በተደጋጋሚ ጥቅም ላይ የዋለ ሲሆን ከሰሀቦች የአንዱ ስም ከተጻፈ ከአጠገቡ ይቀመጣል:: ትርጉሙም "የአላህ ውዴታ በእርሱ ላይ ይሁን" ማለት ነው::

يتطاولون في البنيان ثم انطلق فلبث مليا ثم قال يا عمر أتدري من السائل؟ قلت :الله ورسوله أعلم قال فإنه جبريل أتاكم يعلمكم دينكم] رواه مسلم

*'የአላህ መልእክተኛ ሆይ! እስኪ ስለኢስላም ይንገሩኝ?'' አለ:: ከዚያም ነብዩ ﷺ[2] 'ኢስላም ማለት፤ ከአላህ በቀር በእውነት የሚመለክ እንደሌለ እና ሙሀመድም ﷺ የአላህ መልዕክተኛ መሆናቸውን መመስከር፤ ሶላትን በተሟላ ሁኔታ መስገድ፣ ዘካን መስጠት፣ የረመዷንን ወር መጾም፣ አቅምህ ከፈቀደ ሀጅ መሄድ ነው'*

*ሰውየዉም 'እውነትህን ነው' አላቸው:: እኛም እንደማያውቅ ሰው ጠይቆ ሲያበቃ 'እውነትህን ነው' በማለቱ ተገረምን:: ከዚያም ወደ ሌሎች ጥያቄዎች አመራ:: 'ስለኢማን ይንገሩኝ?' አላቸው:: ነብዩም ﷺ 'በአላህ በመላእክቶቹ፣ በመጻህፍቱ፣ በመልዕክተኞቹ፣ በመጨረሻው ቀን እንዲሁም ጥሩም ይሁን መጥፎ በአላህ ውሳኔና ፍቃድ (ቀደር) እንደሚከሰት ማመን ነው' በማለት ነገሩት::*

*አሁንም 'እውነትህን ነው' ካላቸው በኋላ 'ስለኢህሳን ይንገሩኝ?' አላቸው:: ነብዩም 'አላህን ልክ እንደምታየው ሆነህ መገዛት ነው፤ አንተ ባታየው እንኳን እሱ ያይሀልና' አሉት:: 'እስኪ ስለቂያማ (ትንሳኤ) ሰአት ይንገሩኝ?' አላቸው:: ስለዚህ ጉዳይ 'ተጠያቂው ከጠያቂው ይበልጥ እውቀት የለውም' የሚል ምላሽ ሰጡት:: ሰውየውም 'እሺ ስለምልክቶቿ ይንገሩኝ?' አላቸው:: 'ሴት ባሪያ አሳዳሪዋን ስትወልድ፤ ጫማ የለሽ፣ ድሃ፣ የተራቆቱ በግ እና ፍየል ጠባቂ የነበሩ ሰዎች በህንፃ ግንባታ ሲፎካከሩ ስታይ' የሚል ምላሽ ሰጡት:: ከዚያም ሰውዬው ወጥቶ ሄደ::*

[2] ይኸኛው ቃል ደግሞ ከነብዩ ሙሀመድ ስም ጎን የሚቀመጥ ሲሆን ትርጉሙም "የአላህ ሰላምና እዝነት በእርሳቸው ላይ ይሁን" ማለት ነው::

*ይህ ከሆነ ከተወሰኑ ቀናት በኋላ፣ የአላህ መልዕክተኛ ﷺ አገኙኝና 'አንተ ኡመር ሆይ! [ባለፈው ሲጠይቅ የነበረውን] ሰው ታውቀዋለህን?' አሉኝ:: 'አላህና የአላህ መልእክተኛ ያውቃሉ' አልኳቸው:: 'እንሆ እሱ ጅብሪል ነው:: ዲናችሁን ሊያስተምር [በሰው ተመስሎ] መጥቶ ነው' አሉኝ::* ሙስሊም ዘግበውታል [3]

ጅብሪል ለረሱልﷺ ላቀረባቸው አምስት ጥያቄዎች መልስ ካገኘ በኋላ፣ ፈጥኖ በመውጣት ከሰሃቦች ተሰወረ:: ሰው ተመስሎ በመጣው ጅብሪል ሁኔታና እያወቀ በመጠየቁ ግራ የተጋቡት ሶሀቦች፣ ማንነቱን ለማወቅ ተከትለው ወጡ፤ ሆኖም ዱካው የለም፤ የውሀ ሽታ ሆነባቸው::

ቀደም ሲል የቀረበው «ሀዲሱ ጅብሪል» ወይም በአሊሞች አገላለፅ «የሀዲሶች ሁሉ እናት» በታላቅ ቁምነገር የተሞላ ነው:: ነብዩﷺ ስለእስልምና ማዕዘናት (ስለአርካነል ኢስላም)፣ ስለእምነት ማዕዘናት (ስለአርካነል ኢማን)፣ ስለኢህሳን እና የቂያማ ምልክቶች ተጠይቀው ምላሽ የሰጡበት ከመሆኑም በላይ፣ ሀዲሱ የዲናችን ጥቅል መርሆዎች የተካተቱበት ነው::

ዲን ደረጃዎች ያሉት፤ ሰዎች ከነዚህ ደረጃዎች አንፃር ሲታዩ ወይም ሲለኩ አንድ አይደሉም፤ ከመካከላቸው ሙስሊም፣ ከዚያም ሙእሚን፣ ከዚያም ሙህሲን አለ:: አንድ ሰው ሙስሊም ሳይሆን ሙዕሚን፣ ሙዕሚን ሳይሆን ሙህሲን ሊሆን አይችልም:: እነዚህ ደረጃዎች አንዱ በአንዱ ላይ የተነባበሩና አንዱ ሌላውን ተከትሎ የሚመጡ ናቸው::

ከዚህ በመቀጠል በሀዲሱ ውስጥ ያሉትን ዋና ዋና ነጥቦች አንድ በአንድ በመለየት የተሰጣቸውን ትንታኔ ወይም ማብራሪያ እናያለን::

---

[3] በዚህ መፅሀፍ ውስጥ የተጠቀሱት ሀዲሶች በሙሉ በሶሂህ ወይም በሀሰን ደረጃ ተቀባይነት ያላቸው ናቸው::

# የሀዲሱ ትንተና (ሸርህ)

በመጀመሪያ ጅብሪል ወደ ረሱልﷺ ሲመጣ የነበረውን ሁኔታና በሰሀቦች ላይ ያደረውን ስሜት፣ የጅብሪልን አለባበስና የአቀማመጥ ስርአት በተመለከተ የተሰጠው ማብራሪያና ከዚህ የምንቀስመው ትምህርት፤ በመቀጠልም በረሱልﷺ እና በጅብሪል መካከል የተደረገው ዋናው የጥያቄና መልስ ሂደት ማብራሪያ ይቀርባል።

## 1.«ከነብዩ ዘንድ ተቀምጠን እያለ...»

ከነብዩ ጋር በመቀመጥ የተለያዩ ኢልሞችን (እውቀትን) መቅሰም የሱሀቦች አንዱ ተግባር ነበር። በአንድ ወቅት ስለዲናቸው ነብዩንﷺ እየጠየቁ ባለበት ሁኔታ፣ ከዚህ በፊት አይተውት የማያውቁት እንግዳ ሰው ብቅ አለ። ግለሰቡን አንድም የሚያውቀው ሰው የለም። እንግዳ ነው እንዳይሉ፣ መንገደኛ መሆኑን የሚጠቁም ምንም አይነት ምልክት አይታይበትም፤ ልብሱ አላደፈም፤ ይልቁንም በጣም ነጭ ነው። ስንቅ አልያዘም፤ የመጓጓዣ እንስሳም የለውም። ይህ ሰው ለሶሀቦቹ ትንግርት ሆነባቸው። «ሰውዬው» ጅብሪል ነበር። ጅብሪል በተፈጥሮ ቅርፁ ወደ ነብዩﷺ ከመጣበት ጊዜ ይልቅ፣ በሰው ተመስሎ የመጣበት ጊዜ ይበልጣል። አንድ መላኢካ በተፈጥሮ ቅርፁ ወደ ምድር ቢወርድ፣ የሰው ልጅ መላኢካውን በአይኑ ማየት ይቅርና፣ በምድር ገጽ ላይም መኖር አይችልም ነበር።

መላኢካዎች በተፈጥሮ ቅርፃቸው ለሰው ልጅ በገሀድ የሚታዩ ሆነው ወደ ምድር የሚወርዱት ለሁለት ጉዳዩች ብቻ ነው፡-

1. የሰው ልጅ በሚሞት ጊዜ፤ (ነፍሱን ለማውጣት)
2. በከሀዲዎች ላይ መቅሰፍታዊ ቅጣት ለማድረስ።

አላህ እንዲህ ይላል፤

﴿يَوْمَ يَرَوْنَ الْمَلَائِكَةَ لَا بُشْرَىٰ يَوْمَئِذٍ لِّلْمُجْرِمِينَ وَيَقُولُونَ حِجْرًا مَّحْجُورًا ﴿٢٢﴾﴾ الفرقان:٢٢

***«መላእክትን በሚያዩበት ቀን በዚያ ጊዜ ለአመፀኞች ምስራች የላቸውም፤ መላዕክትም፤ ዛሬ ነጻ መውጣታችሁ የተከለከለ እርም ነው ይላሉ።»*** *(ፉርቃን፣ 22)*

ነብዩ ﷺ በህይወት ዘመናቸው ጅብሪልን በተፈጥሮ ቅርፁ ሁለት ጊዜ አይተውታል። ይኸውም፡-

**1ኛ-** ከመካ ሙሽሪኮች (አጋሪዎች) በደረሰባቸው ስቃይ ወደ መካ አሸዋማ ሸለቆ ሸሽተው እያለ ጅብሪል የተፈጥሮ ቅርፁን ይዞ በሰማይ አድማስ ተንጣሎ አረጋግቷቸዋል።

**2ኛ-** በለይለተል ሚዕራጅ ሲድረተል ሙንተሀ (የጀነት ዛፍ) አጠገብ በተፈጥሮ ቅርፅ አይተውታል።

አላህ እንዲህ ይላል፡-

﴿ وَلَقَدْ رَءَاهُ نَزْلَةً أُخْرَىٰ ۝١٣ عِندَ سِدْرَةِ ٱلْمُنتَهَىٰ ۝١٤ ﴾ النجم: ١٣ - ١٤

***«በሌላይቱም መውረድ ጊዜ በርግጥ አይቶታል። በመጨረሻይቱ ቁርቁራ(የሰዎች እውቀት መጨረሻ በሆነ ቦታ) አጠገብ።»*** *(ነጅም፣ 13-14)*

### 1. «ልብሱ በጣም ነጭ... የሆነ ግለሰብ ብቅ አለ።»

የልብሱ በጣም መንፃት የተገለፀው፣ ንፅህናው በከፍተኛ ሁኔታ የተጠበቀ መሆኑን ለማሳየት ነው። ከዚህ የጅብሪል አለባበስ የምንማረው፣ አንድ ተማሪ ከመምህሩ ዘንድ ትምህርት ለመከታተል በሚሄድበት ጊዜ በተቻለው መጠን ጥሩ ልብስ መልበስና ንፅህናውን መጠበቅ እንዳለበት ነው። በዚህ አለባበስ ጅብሪል ሶሀቦች ከረሱል ﷺ መጅሊስ በምን አይነት ሁኔታ መምጣት እንዳለባቸው አስተምሯል። ኢስላማዊ የእውቀት መድረክ አላህን ስለመፍራት የምንማርበት ነው። እናም ከአሊሞች ጋር ያለን ግንኙነት ከፍተኛ ዝግጅት ያስፈልገዋል። ኡለሞችን አላህ ባዘዘን መልክ ማላቅ ተገቢ ነው፤ ምክንያቱም ለኡለሞች ክብርና ልቅና ካልሰጠን፣ ከእውቀታቸው ተጠቃሚ ልንሆን አንችልምና።

## 2·«...ከነብዩ ፊት ለፊት ተቀመጠ።»

ከዚህ የጅብሪል የአቀማመጥ ሁኔታ የዲን ተማሪዎች ሊቀስሙት የሚገባ ትምህርት አለ። ከፍ ሲል ስለአለባበስና ንፅህና አጠባበቅ የተገለፀው እንደ ተጠበቀ ሆኖ፣ አንድ ተማሪ ከከመምህሩ እውቀት ለመውሰድ ሲቀመጥ፣ እውቀት በቀጥታ እንዲደርሰው ፊት ለፊት መቀመጥ እንዳለበት እንዲሁም መቀለድ፣ አላግባብ መዟዟርና በተለያዩ ነገሮች መጠመድ እንደማይገባው፤ ይልቁንም ከትምህርቱ አንድም ነጥብ እንዳያመልጠው ሁለንተናውን፤ አካሉን፣ አእምሮውንና ስሜቱን ለትምህርቱ መስጠት እንዳለበት ያስተምረናል።

## 3·«...ጉልበቶቹን ወደ ነብዩ ጉልበቶች በማስጠጋት...»

ከዚህ የምንማረው ተማሪ ከመምህሩ የሚፈስለትን እውቀት ከምንጩ ለመቅዳት ወደ መምህሩ ተጠግቶ ወይም በጣም ቀረብ ብሎ መቀመጥ እንዳለበት ነው። በርቀት ከሆነ የሚሰጠውን ትምህርት በወጉ ላያዳምጥ ወይም ላይሰማ ይችላል። ሶሀቦች ከነብዩ ﷺ የሚሰጣቸውን ትምህርት የሚገበዩት ወደ እሳቸው በሚገባ በመቅረብና አተኩረው በመከታተል ነበር።

## 4·«...እጆቹን ከጭኖቹ ላይ በማስቀመጥ...»

ጅብሪል እጆቹን ከእራሱ ጭን ላይ አኖረ። ከዚህ የምንረዳው ተማሪ እውቀት በሚቀስምበት ጊዜ የተረጋጋና ስርዓት የያዘ መሆን እንዳለበት ነው። እንቅስቃሴ ማብዛት፣ ወዲያ-ወዲህ መዟዟር እና በተለያዩ ነገሮች መጠመድ የለበትም።

ጅብሪል ጥያቄውን ያቀረበው በተሟላ ሁኔታ ተስተካክሎ ከተቀመጠ በኋላ ነው። ስለሆነም አንድ ሰው አሊምን መጠየቅ ያለበት፣ ተረጋግቶ ከተቀመጠ በኋላ ነው። እንደ መጣ ተንደርድሮ ጥያቄ ማቅረብ የለበትም። መጀመሪያ በስርዓት መቀመጥ፤ ከዚያም ሊጠይቅ የፈለገውን ጉዳይ በስርአት ማቅረብ ይገባዋል።

# የጥያቄና መልስ ሂደት

በጅብሪልና በረሱልﷺ መካከል ከተካሄደው የጥያቄና መልስ ሂደት መረዳት እንደሚቻለው፣ ጅብሪል አምስት ጥያቄዎችን ለረሱልﷺ ያቀረበ ቢሆንም፣ ነብዩን የጠየቀው መልሱን እያወቀ ነበር:: ሆኖም ይህን ያደረገው፣ እሳቸውን ለመፈታተን አይደለም፤ ሶሀቦችን ለማስተማር እንጂ::

ከዚህ የምንረዳው በጥያቄና መልስ አቀራረብ ሰዎችን ማስተማር እንደሚቻል ነው፤ ምክንያቱም ይህ አቀራረብ አእምሮን አንቂ ነው:: መጀመሪያ የዲን መምህር ተማሪዎቹን ለማነቃቃት ይጠይቃል:: ተማሪዎቹ መልሱን ለማግኘት የአእምሯቸውን ጓዳ መፈተሽ ሲጀምሩ ይነቃቃሉ:: ከዚያም መምህሩ ይመልሳል:: በቀጥታ ትምህርቱን መስጠት ከጀመረ ግን ተማሪው አይነቃቃም:: ሰለዚህ ከመማር-ማስተማር ስልቶች መካከል በጣም ጠቀሚው በጥያቄና መልስ ማስተማር ነው::

ጅብሪል ለረሱል ﷺ ያቀረባቸው ጥያቄዎች በድምሩ አምስት ናቸው:-

1. *'የአላህ መልእክተኛ ሆይ! እስኪ ስለኢስላም ይንገሩኝ?"*
2. *'ስለኢማን ይንገሩኝ?'*
3. *'ስለኢህሳን ይንገሩኝ?'*
4. *'እስኪ ስለቂያማ (ትንሳኤ) ሰአት ይንገሩኝ?'*
5. *'ስለ(ትንሳኤ) ምልክቶቿ ይንገሩኝ?*

ለእነዚህ አምስት ጥያቄዎች የተሰጡት ምላሾችና ማብራሪያቸው በሚከተለው መንገድ ቀርቧል::

## የመጀመሪያው የጅብሪል ጥያቄ

**«...የአላህ መልእክተኛ ሆይ! እስኪ ስለኢስላም ይንገሩኝ?»**

ይህ ጥያቄ አንድ ሙስሊም ስለኢስላም መሰረታዊ ማዕዘናት ማወቅ ያለበት መሆኑን ያስረዳል፤ ወደ ኢስላም መጠጋቱ ወይም

*«ሙስሊም ነኝ» ማለቱ ብቻ በቂ አይደለምና:: ኢስላምን ጠንቅቆ ሳያውቅ እንዴት ኢስላማዊ ተግባራትን ሊፈፅም ይችላል? አንድን ነገር ሳያውቁ መተግበር አይቻልም::*

ነብያችን ﷺ ለጅብሪል የሰጡት ምላሽ የሚከተለው ነው፤

**‹‹ኢስላም ማለት** [1] **ላኢላሀ ኢለላህ፣ ሙሀመድ ረሱሉላህ ብሎ መመስከር፤** [2] **ሶላትን መስገድ፤** [3] **ዘካን መስጠት፤** [4] **የረመዷን ወርን መቋቫፆምና** [5] **አቅም ላለው ሰው ለሀጅ ስራ የአላህን ቤት መጎብኘት ነው::››**

*ረሱል ﷺ ከሰጡት ምላሽ የምንረዳው ኢስላም በእነዚህ አምስት መሰረቶች ላይ የተገነባ መሆኑን ነው:: አንድ ሙስሊም በልቡ አምኖ እነዚህን አምስት የእስልምና መሰረቶች የመፈፀም ግዴታ አለበት:: ሆኖም ከእነዚህ አምስት የኢስላም መሰረቶች መካከል ላኢላሀ ኢለላህ፣ ሙሀመድ ረሱሉላህና ሶላትን ቢተውና ረመዷንን ቢጾም ዘካን ቢሰጥ ሀጅ ቢያደርግና እንደ እውነት መናገር፣ በመልካም ማዘዝ፣ ከመጥፎ ነገሮች መከልከል፣ ዝምድናን መቀጠል፣ ወዘተ. ያሉ ዋጅቦችንና ተወዳጅ ነገሮችን ቢሰራ ስራው ተቀባይነት የለውም::*

በሌላ በኩል እነዚህ መሰረቶች ወይም ማዕዘናት ዋና ምሰሶዎቹ ናቸው እንጂ፣ ኢስላምን በሁለንተናዊ መልኩ አያካትቱም:: ኢስላም በጣም ሰፊ ነው:: አላህ ያዘዘውም፣ የከለከለውም ሁሉ ከኢስላም ነው:: አላህ እንዲህ ይላል፤

﴿يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ ٱدۡخُلُواْ فِي ٱلسِّلۡمِ كَآفَّةً وَلَا تَتَّبِعُواْ خُطُوَٰتِ ٱلشَّيۡطَٰنِۚ إِنَّهُۥ لَكُمۡ عَدُوٌّ مُّبِينٌ ٢٠٨﴾ البقرة: ٢٠٨

***‹‹እናንተ ያመናችሁ ሆይ! ሁላችሁም በመታዘዝ(በኢስላም) ውስጥ ግቡ፤ የሰይጣንንም እርምጃ አትከተሉ፤ እርሱ ለናንተ ግልፅ ጠላት ነውና::››*** *(በቀራህ፣ 208)*

ኢስላም በርካታ ጉዳዮችን የሚያካትት መሆኑን ለማመላከት፣ ረሱልም ﷺ በሀዲሳቸው እንዲህ ብለዋል፤

"المسلم من سلم المسلمون من لسانه ويده" رواه البخاري ومسلم

*‹‹ሙስሊም ማለት ሙስሊሞች ከእጁና ከምላሱ ሰላም የሆኑለት ሰው ነው…››*

«ኢስላም» ማለት - ሼይኹል ኢስላም እንደ ገለጹት - አምልኮትን ፍፁም ለአላህ ብቻ በማድረግ (በተውሂድ) ታዛዥነትን ማሳየትና ለአላህ ትእዛዝ እጅ መስጠት እንዲሁም ከማጋራትና ከሙሽሪኮች (አጋሪዎች) መራቅ ማለት ነው። ጥቅል ትርጓሜው ይህ ነው።

ረሱል ﷺ ለጅብሪል የገለጿቸው አምስቱ የኢስላም ማዕዘናት ዝርዝር ማብራሪያ እንደሚከተለው ቀርቧል፦

## የመጀመሪያው ማዕዘን

### *ሁለቱ የምስክርነት ቃሎች (ሸሀደታን)*

*«ሸሀደቱ አንላኢላሀ ኢለላሁ»* ብሎ መመስከር ማለት አላህን በብቸኝነት ማምለክ ግዴታ መሆኑን መመስከር ማለት ነው። *«ሙሀመድ ረሱሉላሁ»* ብሎ መመስከር ደግሞ ነብዩን ﷺ በመከተል እና በመታዘዝ ብቸኛ ማድረግ ማለት ነው፤ ምክንያቱም እርሳቸው ከአላህ የወረደው መልዕክት ብቸኛ አድራሽ ናቸውና። እነዚህ ሁለት የምስክርነት ቃሎች ተነጣጥለው የሚታዩ አይደሉም። አንድ ሰው አንደኛውን ትቶ፣ በሌላኛው ብቻ ቢመሰክር ምስክርነቱ ተቀባይነት የለውም። ከዚህ በተጨማሪ ሁለቱ የምስክርነት ቃላት ተቀባይነት የሚኖራቸው በአፍ ስለተነገሩ ብቻ ሳይሆን፣ በተግባር ስራ ላይ ሲውሉ ጭምር መሆን አለበት።

«**አሽሀዱ አንላኢላሀ…**» በሚለው ቃል ውስጥ፣ «ላ» የምትለው ቃል አፍራሽ ስትሆን፣ ከአላህ ውጭ ለማንም የሚፈጸም አምልኮትን የምታወግዝ ነች። «ኢለላህ» የሚለው ሀረግ ደግሞ በእውነት ሊመለክ የሚገባው አላህ ብቻ መሆኑን ያረጋግጣል። «ኢላህ» የሚለው ቃል ትርጉሙ «መዕቡድ» ወይም «የሚመለክ» ማለት ነው። ስለሆነም «ላኢላሀ ኢለላህ» ማለት «*ከአላህ በስተቀር በእውነት የሚመለክ የለም*» ማለት

ነው። ከአላህ ውጭ የሚመለክ ሁሉ የውሸት ተመላኪ በመሆኑ፣ ይህ የምስክርነት ቃል የውሸት ተመላኪን ሁሉ ውድቅ ያደርጋል።

በሌላ በኩል አሁን በአለንበት ዘመን *«ላኢላሀ ኢለላህ»* በማለት ከመሰከሩ በኋላ፣ ከአላህ ውጭ ያሉ አካላትን፤ የሞቱ ሰዎችን ጭምር መንፈሳዊ እርዳታ በመጠየቅ የሚያመልኩ ሰዎች አሉ። በሽርክ እድፍ ተበክለው እያለ፣ *«ሙስሊም ነን»* በማለት ይሞግታሉ። ስለዚህም ላኢላሀ ኢለላህን በተገቢው መንገድ አላሉትም፤ ለአፍ ያህል ቢሉም በሽርክ ተግባር አፍርሰውታልና።

*«ሙሀመድ የአላህ መልዕክተኛ ናቸው»* ብሎ መመስከር ማለት ደግሞ፣ *«ሙሀመድ ﷺ ወደ ሰዎችና ጅኖች አላህ ﷻ መልዕክተኛ አድርጎ የላካቸው መሆኑን አረጋግጣለሁ»* ማለት ነው። በዚህ የምስክርነት ቃል ሙሀመድ ﷺ የአላህ መልእክተኛ መሆናቸውን ስናረጋግጥ በውስጥም፣ በውጭም መሆን አለበት። ይህም ማለት በልብ አምኖ በምላስ መናገር ማለት ነው። አንድ ሰው በምላሱ የአላህ መልዕክተኛ መሆናቸውን አረጋግጦ፣ በልቡ ተቃዋሚ ከሆነ ይህ ሰው «ሙናፊቅ» ይባላል፡-

﴿إِذَا جَآءَكَ ٱلۡمُنَٰفِقُونَ قَالُواْ نَشۡهَدُ إِنَّكَ لَرَسُولُ ٱللَّهِۗ وَٱللَّهُ يَعۡلَمُ إِنَّكَ لَرَسُولُهُۥ وَٱللَّهُ يَشۡهَدُ إِنَّ ٱلۡمُنَٰفِقِينَ لَكَٰذِبُونَ ١﴾ المنافقون: ١

***‹‹መናፍቃን በመጡህ ጊዜ ‹አንተ የአላህ መልእክተኛ መሆንህን በእርግጥ (ምለን) እንመሰክራለን› ይላሉ። አላህም አንተ በእርግጥ መልእክተኛው መሆንህን ያውቃል። አላህም መናፍቃን (‹ከልብ እንመሰክራለን› በማለታቸው) ውሸታሞች መሆናቸውን ይመሰክራል።››*** (አል-ሙናፊቁን፣ 1)

በዚህ የቁርአን አንቀጽ ውስጥ የተጠቀሱት ሙናፊቆች፣ ሙሃመድ ﷺ የአላህ መልእክተኛ መሆናቸውን በአንደበታቸው አረጋግጠዋል፤ መስክረዋል። ነገር ግን የምስክርነት ቃላቸው ውሸት ነው፤ ምክንያቱም በአፍ ቢናገሩም፣ በልባቸው እውነተኛ መስካሪዎች ስላልሆኑ። በአንደበታቸው የሚመሰክሩት

ከሙስሊሞች ጋር ተመሳስሎ ለመኖር፣ ከዚህች አለም ምድራዊ ጥቅም ተቋዳሽ ለመሆንና ከሙስሊሞች ጥቃት ለመዳን መደበቂያ ሽፋን ለማድረግ ብቻ ነው እንጂ በልቦቻቸው ከሀዲዎች ናቸው።

ልክ እንደዚሁ በልቡ መስክሮ (ተቀብሎ)፣ በአንደበቱ ለመናገር «እምቢ» ያለ ሰው «ሙስሊም» አይባልም። የመካ ሙሽሪኮች የረሱልን መልዕክተኛነት በልባቸው ይመሰክሩ ነበር። አላህ እንዲህ ይላል፡-

﴿قَدْ نَعْلَمُ إِنَّهُۥ لَيَحْزُنُكَ ٱلَّذِى يَقُولُونَ ۖ فَإِنَّهُمْ لَا يُكَذِّبُونَكَ وَلَٰكِنَّ ٱلظَّٰلِمِينَ بِـَٔايَٰتِ ٱللَّهِ يَجْحَدُونَ ﴿٣٣﴾﴾ الأنعام: ٣٣

*‹‹እነሆ ያ የሚሉህ ነገር እንደሚያሳዝንህ በርግጥ እናውቃለን። እነርሱም /በልቦቻቸው/ አያስተባብሉህም። ግን በዳዮች በአላህ አንቀጾች ይክዳሉ።››* (አንዓም፣ 33)

በነብዩ ዘመን የነበሩት ሙናፊቆችና ሙሽሪኮች፣ ረሱል የአላህ መልዕክተኛ መሆናቸውን ከልባቸው በርግጠኝነት ተረድተዋል። ነገር ግን ይህን ያወቁትን ሀቅ ይፋ አውጥተው እንዳይናገሩ የከለከላቸው የተጠናወታቸው ኩራትና ህሊናቸውን እስከማወር የደረሰው ለአማልክቶቻቸው የነበራቸው ስሜትና ፍቅር ነበር።

በወቅቱ የነበሩትን የአይሁዶችን ሁኔታም ብንመለከት እውነታው ከዚህ የተለየ አልነበረም። በልባቸው ነቢዩ ሙሀመድ ﷺ የአላህ መልዕክተኛ መሆናቸውን መስክረዋል። ነገር ግን ከአንደበታቸው የምስክርነት ቃል ሊወጣ አልቻለም፤ ካዱ። አላህ እንዲህ ይላል፤

﴿ٱلَّذِينَ ءَاتَيْنَٰهُمُ ٱلْكِتَٰبَ يَعْرِفُونَهُۥ كَمَا يَعْرِفُونَ أَبْنَآءَهُمْ ۖ وَإِنَّ فَرِيقًا مِّنْهُمْ لَيَكْتُمُونَ ٱلْحَقَّ وَهُمْ يَعْلَمُونَ ﴿١٤٦﴾﴾ البقرة: ١٤٦

*‹‹እነዚያ መጽሃፍን የሰጠናቸው፣ ወንዶች ልጆቻቸውን እንደሚያውቁ (ሙሃመድን) ያውቁታል። ከነሱም የተወሰኑ ክፍሎች እነርሱ የሚያውቁ ሲሆኑ እውነቱን በርግጥ ይደብቃሉ። ›› (አል በቀራህ 146)*

ስለሆነም ምስክርነት የግድ በአንደበትም፣ በልብም መሆን ይኖርበታል። ምክንያቱም ከላይ እንደተገለፀው ሙሽሪኮችና

አይሁዶች በልባቸው መስክረዋል፡፡ ነገር ግን «በአንደበታችን የምስክርነትን ቃል አንናገርም» አሉ፡፡ «ገቢአችን ይነጥፋል»፣ «ስልጣናችንን እንነጠቃለን» ብለው በመፍራት ወይም በረሱል ላይ ባደረባቸው ምቀኝነትና በተጠናወታቸው ኩራት እንዲሁም በሌሎች የተለያዩ መጥፎ ምክንያቶች የተነሳ አንደበታቸው ተሳሰረ፤ ሀቁን መናገር አልቻሉም፡፡

በሌላ በኩል አንደበታቸው የሙሀመድን ﷺ መልዕክተኛነት ከመሰከረ የግድ ሊከተላቸው ይገባል፡፡ ይህ ካልሆነ ግን በአንደበት የሚሰጥ ምስክርነት ብቻውን ተቀባይነት አይኖረውም፤

﴿فَإِن لَّمْ يَسْتَجِيبُوا۟ لَكَ فَٱعْلَمْ أَنَّمَا يَتَّبِعُونَ أَهْوَآءَهُمْ ۚ وَمَنْ أَضَلُّ مِمَّنِ ٱتَّبَعَ هَوَىٰهُ بِغَيْرِ هُدًى مِّنَ ٱللَّهِ ۚ إِنَّ ٱللَّهَ لَا يَهْدِى ٱلْقَوْمَ ٱلظَّٰلِمِينَ ﴿٥٠﴾﴾ القصص: ٥٠

***‹‹እሺ ባይሉህም የሚከተሉት ዝንባሌዎቻቸውን ብቻ መሆኑን እወቅ፤ ከአላህም የሆነ መመሪያ ሳይኖረው ዝንባሌውን ከተከተለ ሰው ይበልጥ የጠመመ አንድም የለም፣ አላህ በደለኞች ህዝቦችን አይመራምና፡፡››*** *(ቀሰስ፣ 50)*

﴿يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُوٓا۟ أَطِيعُوا۟ ٱللَّهَ وَأَطِيعُوا۟ ٱلرَّسُولَ وَأُو۟لِى ٱلْأَمْرِ مِنكُمْ ۖ﴾ النساء: ٥٩

***‹‹እናንተ ያመናችሁ ሆይ! አላህን ተገዙ፤ መልዕክተኛውንና ከናንተም የስልጣን ባለቤቶችን ታዘዙ፡፡»*** *(ኒሳእ፣ 59)*

﴿يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُوٓا۟ أَطِيعُوا۟ ٱللَّهَ وَرَسُولَهُۥ وَلَا تَوَلَّوْا۟ عَنْهُ وَأَنتُمْ تَسْمَعُونَ ﴿٢٠﴾﴾ الأنفال: ٢٠

***«እናንተ ያመናችሁ ሆይ! አላህን እና መልእክተኛውን ታዘዙ፤ እየሰማችሁ ከርሱ አትሽሹ፡፡»*** *(አንፋል፣ 20)*

﴿يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُوٓا۟ أَطِيعُوا۟ ٱللَّهَ وَأَطِيعُوا۟ ٱلرَّسُولَ وَلَا تُبْطِلُوٓا۟ أَعْمَٰلَكُمْ ﴿٣٣﴾﴾ محمد: ٣٣

***«እናንተ ያመናችሁ ሆይ! አላህን ተገዙ፡፡ መልእክተኛውንም ታዘዙ፤ ስራዎቻችሁንም አታበላሹ፡፡»*** *(ሙሀመድ፣ 33)*

﴿مَّن يُطِعِ ٱلرَّسُولَ فَقَدْ أَطَاعَ ٱللَّهَ ۖ وَمَن تَوَلَّىٰ فَمَآ أَرْسَلْنَٰكَ عَلَيْهِمْ حَفِيظًا ﴿٨٠﴾﴾ النساء: ٨٠

*«መልእክተኛውን የሚታዘዝ ሰው በርግጥ አላህን ታዘዘ፤ ከትእዛዝም የሸሸ ሰው (ኢያሳስብህ) በነርሱ ላይ ጠባቂ አድርገን አላክንህም።» (ኒሳእ፣ 80)*

﴿ وَأَطِيعُوا۟ ٱللَّهَ وَٱلرَّسُولَ لَعَلَّكُمْ تُرْحَمُونَ ﴿١٣٢﴾ ﴾ آل عمران: ١٣٢

*«ይታዘንላችሁም ዘንድ አላህንና መልእክተኛውን ታዘዙ።» (አልዒምራን፣132)*

﴿قُلْ أَطِيعُوا۟ ٱللَّهَ وَأَطِيعُوا۟ ٱلرَّسُولَ ۖ فَإِن تَوَلَّوْا۟ فَإِنَّمَا عَلَيْهِ مَا حُمِّلَ وَعَلَيْكُم مَّا حُمِّلْتُمْ ۖ وَإِن تُطِيعُوهُ تَهْتَدُوا۟ ۚ وَمَا عَلَى ٱلرَّسُولِ إِلَّا ٱلْبَلَٰغُ ٱلْمُبِينُ ﴿٥٤﴾ ﴾ النور: ٥٤

*«አላህን ተገዙ፤ መልእክተኛውንም ታዘዙ። ብትሸሹም (አትኅዱትም) በርሱ ላይ ያለበት እንዲያደርስ የታዘዘውን ማድረስ ብቻ ነው። በናንተም ላይ ያለባችሁ በመታዘዝ ግዴታን መወጣት ብቻ ነው። ብትታዘዙትም ትመራላችሁ፤ መልእክተኛው ላይ ግልጽ ማድረስ እንጂ ሌላ የለበትም በላቸው» (ኑር፣ 54)*

ለአንድ ሙስሊም ረሱልﷺ የአላህ መልእክተኛ መሆናቸውን በልብ አምኖ በአንደበት መመስከሩ ብቻ በቂ አይደለም፤ በቃል የሰጠውን የምስክርነት ቃል በተግባር ማረጋገጥ ይኖርበታል። ይህ ሊሆን የሚችለው ደግሞ ለረሱል ﷺ ታዛዥ ሲሆን ብቻ ነው። ቁርአን አንዳንድ ጊዜ ረሱልን የመታዘዝን ጉዳይና አስፈላጊነት፣ አላህን ከመታዘዝ ጋር አጣምሮ፣ አንዳንዴ ደግሞ ለብቻው ያመጣዋል። ይህ የሚያመላክተው አዲስ ኢባዳ (አምልኮ) ሳንፈጥርና ከተሰጠን ኢባዳ ላይ ምንም ሳንቀንስ ረሱልን ﷺ መታዘዝና መከተል አማራጭ የሌለው መሆኑን ነው።

ስለሆነም እስልምና የተለያዩ በዲን ላይ የተጨመሩ ፈጠራዎችን እርግፍ አድርጎ መተውን፣ ረሱልን መታዘዝንና መከተልን ግድ ይላል። መልካም የተባለ ነገር በሙሉ ሊገኝ የሚችለው ነብዩንﷺ በመከተል ነው። በአንፃሩ እርሳቸው እንዲሰራ ያላዘዙት ነገር በሙሉ ሸር እንጅ መልካም አይደለም፤

የስራው ባለቤት *«መልካም ጭማሬ ነው፣ ምን አለበት?»* ቢልም እንኳን። የትክክለኛ ሙስሊሞች መልስ መሆን የሚገባው፣ *«አይደለም፤ ይልቁንም ይህ ፈጠራ (ቢድዓ) ነው። ቢድዓ ደግሞ ከአላህ ዘንድ ተቀባይነት የለውም። ስለሆነም ይህ ተግባርህ ኸይር ሳይሆን ሸር ነው»* የሚል ነው። አዎ - ለዚህ አይነቱ ሰው፣ *«አንተ በርግጥ ወደ አላህ የሚያቃርብህን ተግባር ሳይሆን፣ ከአላህ የሚያርቅህን ተግባር ነው እየፈፀምክ ያለኸው»* እንለዋለን።

ነብያችን ﷺ በሀዲሳቸው እንዲህ ብለዋል:

عن عائشة قالت قال رسول الله ﷺ (من أحدث في أمرنا هذا ما ليس منه فهو ردٌّ") رواه البخاري ومسلم

‹‹በዚህ በጉዳያችን (በዲናችን) ከእርሱ ያልሆነን ነገር የፈጠረ (ስራው) ተመላሽ ነው።››

ቡኻሪና ሙስሊም ዘግበውታል። በሌላ ተመሳሳይ ሀዲስ :-

عن عائشة رضي الله قالت قال رسول الله ﷺ (من عمل عملاً ليس عيه أمرنا فهو رد) رواه مسلم

‹‹ትዕዛዛችን የሌለበትን ስራ የሰራ (ስራው) ተመላሽ ነው።›› ሙስሊም ከዓኢሻ ዘግበውታል።

«وَإِيَّاكُمْ وَمُحْدَثَاتِ الأُمُورِ فَإِنَّ كُلَّ بِدْعَةٍ ضَلاَلَةٌ » رواه أبوداود والترمذي من حديث العرباض ابن سارية

***‹‹በዲን ላይ ከሚደረግ ፈጠራ አደራ ተጠንቀቁ! ማንኛውም በዲን ላይ የሚደረግ ፈጠራ ቢድዓ ነው፤ ማንኛውም ቢድዓ ደግሞ ጥመት ነው።››***[4]

ስለሆነም አንድ ሙስሊም እምነቱና የአምልኮ ተግባሩ ተቀባይነት እንዲኖረው፣ *«ሙሀመድ ﷺ የአላህ መልዕክተኛ*

[4] አቡዳውድ፣ቲርሚዚይና ኢብን ማጀህ ዘግበውታል

*ናቸው»* ብሎ ከመመስከር ባሻገር፣ ቢድዓን ወይም በዲን ላይ *የሚደረጉ ፈጠራዎችን* እርግፍ አድርጎ *መተውና መል* በዕክተኛዉ ፈለግ ላይ ብቻ መወሰን ይኖርበታል። በተጨማሪም የተናገሩትን «እውነት» ብሎ *መቀበል*፣ *ያዘዙትን መታዘዝና* የከለከሉትን *መከልከል* አለበት።

በአንፃሩ አንድ የአላህ ባሪያ በታዘዘው መሰረት መተግበሩ ብቻ በቂ አይሆንም፤ እርሳቸው የመጡበትን ሙሉ በሙሉ «እውነት» ብሎ *መቀበል* አለበት። ለአብነት *ያህል* ስለመጪው አለም ምንዳ ወይም ቅጣት ከተናገሩት ውስጥ አንዱን እንኳን ቢያስተባብል ይህ ሰው ንፍቅና ውስጥ ነው ያለው። በመልዕክተኛውﷺ ዘመን የነበሩት ሙናፊቆች ሶላት ይሰግዱ፣ ረመዷንን ይፆሙ፣ ሀጅ ያደርጉና ለጅሀድ ይወጡ ነበር። ነገር ግን ረሱል በመጡበት መልዕክት «እውነት» ብለው የተቀበሉ አልነበሩም። ስለዚህ አንድ ሰው እውነተኛ ሙስሊም ሊሆን ዘንድ፣ በነብዩﷺ እና ይዘውት በመጡት መልእክት ላይ ቅንጣት *ያህል* ጥርጣሬ ሊኖረው አይገባም። አላህ እንዲህ ይላል፡-

﴿وَمَآ ءَاتَىٰكُمُ ٱلرَّسُولُ فَخُذُوهُ وَمَا نَهَىٰكُمْ عَنْهُ فَٱنتَهُوا۟ ۚ وَٱتَّقُوا۟ ٱللَّهَ ۖ إِنَّ ٱللَّهَ شَدِيدُ ٱلْعِقَابِ ﴿٧﴾﴾ الحشر:٧

«… ***መልእክተኛውም የሰጣችሁን (ማንኛውንም) ነገር ያዙት፣ ከርሱ የከለከላችሁን ነገር ተከልከሉ፤ አላህንም ፍሩ፣ አላህ ቅጣተ ብርቱ ነውና።»*** ሀሽር፣ 7

# ሁለተኛው ማዕዘን

## *ሶላትን በተሟላ ሁኔታ መስገድ*

ይህ የኢስላም ማዕዘን በሀያ አራት ሰዓታት ውስጥ አምስት ወቅት ሶላትን ደንቡን ጠብቆ መስገድን የሚመለከት ነው፡ ሰላትን በተሟላ ሁኔታ ልትሰግድ ማለት ትርጉሙ ምንድን ነው? ነብዩ ﷺ ለጅብሪል ስለኢስላም ሲያስረዱ፣ «ሶላት ልትሰግድ» አላሉትም። እሳቸው ያሉት «ሶላትን ቀጥ አድርገህ ልታቆም» (በተሟላ ሁኔታ ልትሰግድ) ነው ያሉት። ስለዚህ የተፈለገው የሶላትን ቅርፅ ማስገኘት ብቻ አይደለም። ሶላታችንን የአላህ

መልእክተኛ *«እኔ እንደምሰግደው አድርጋችሁ ስገዱ»* ባሉት መሰረት መስገድ ይኖርብናል።

«ሶላትን ቀጥ አድርገህ ልታቆም» የሚለው አገላለፅ የሚከተሉትን መሰረታዊ ሀሳቦች አጣምሮ የያዘ ነው፡-

**አንደኛ** - ነብዩ ﷺ በሰገዱት አይነት፣ ማለትም ምንም አይነት ጭመራ ወይም ቅነሳ ሳያደርጉ መስገድ፤

**ሁለተኛ** - ሶላትን አላህ በደነገገው ወቅትና ሰአት መስገድ፤

عبد الله ابن مسعود قال: سألت النبي صلى الله عليه و سلم أي العمل أحب إلى الله ؟

قال (الصلاة على وقتها) رواه البخاري.

ቡኻሪ ከአብዱላህ ኢብኑ መስዑድ በዘገቡት ሀዲስ፤ ነብዩን ﷺ *«ከአላህ ዘንድ ተወዳጁ ስራ ምንድን ነው?»* ብዬ ጠየኳቸውና *«ሶላትን በወቅቱ መስገድ ነው»* አሉኝ።[5]

**ሶስተኛ** - ሰጋጁ በልቡ ከአላህ ፊት መቆሙን እያሰበና አላህን ፈርቶ መስገድ አለበት፤ ለምሳሌ አንድ ሰው በመስጊድ ውስጥ ሶላት በሚሰግድበት ወቅት ግማሽ ልቡ መስጊድ፣ ግማሽ ልቡ ስራ ቦታው ከሆነ ከሶላቱ ውስጥ በሙሉ ልብ ሆኖ የፈፀመው ብቻ ይያዝለታል። አላህ እንዲህ ይላል፤

﴿قَدۡ أَفۡلَحَ ٱلۡمُؤۡمِنُونَ ۝١ ٱلَّذِينَ هُمۡ فِي صَلَاتِهِمۡ خَٰشِعُونَ ۝٢﴾ المؤمنون: ١ - ٢

***«ምእመናን ፍላጎታቸውን ሁሉ በእርግጥ አገኙ፤ እነዚያ እነሱ በስግደታቸው ውስጥ አላህን ፈሪዎች።»*** *(ሙእሚኑን፣ 1-2)*

ሶላት ገር፣ ቀላልና ጣፋጭ የምትሆነው አላህን ለሚፈሩ ሰዎች ነው። አላህን መፍራት የሶላት ሩህ ነው፤ የአላህ ፍርሀት የሌለበት ሶላት፣ ነፍስ የሌለው አካል ማለት ነው። ምንም አይነት የአላህ ፍርሀት በልቡ ላይ ሳያድር የሰገደ ሰው «ሶላትህን እንደ ገና ስገድ» ባይባልም፣ የሰገደው ሶላት አጅር (ምንዳ) አይኖረውም። ሰዎች ሶላት ሲሰግዱ፣ አጅር የሚያገኙት ለአላህ ባላቸው የፍርሀት መጠን ልክ ነው። ስለሆነም ምንም አጅር

---
[5] ቡኻሪ ዘግበውታል

ሳያገኝ ሶላቱን የሚጨርስ አለ፤ ትንሽ አጅር (ምንዳ) ብቻ አግኝቶ የሚጨርስ አለ። የተሟላ አጅር (ምንዳ) አግኝቶ የሚጨርስም አለ።

**አራተኛ - ሶላትን በጀመዓ መስገድ ለወንዶች።**

በጀመዓ መስገድ በእያንዳንዱ ወንድ ላይ ግዴታ ነው። ነብያችን ﷺ እንዲህ ይላሉ፤

قال رسول الله صلى الله عليه وسلم: "لا صلاة لمن سمع النداء ولم يأته إلا من علة" الحديث

*«ችግር አጋጥሞት ካልሆነ በስተቀር፣ አዛን ሰምቶ ጥሪውን ያልተቀበለ (በመስጊድ ያልሰገደ) ሶላት የለውም።»* [6] ሶላት በየቤቱ ወይም በያሉበት ቦታ መሰገድ ያለበት ቢሆን ኖሮ፣ አዛን (የሶላት ጥሪ) ለምን ተደነገገ? ነገር ግን ወደ መስጊድ ሄዶ ላለመስገድ ምክንያት ያለው ሰው፣ ለምሳሌ ህመምተኛ ከሆነ ወይም በአካባቢው ጀመዓ ወይም መስጊድ ከሌለ ባለበት ቦታ መስገድ ይችላል። ነገር ግን ጤናማ ሆኖ፣ በአካባቢው መስጊድ እያለ ምንም አይነት ሸሪአዊ ምክንያት ሳይኖረው ከቤቱ መስገድ የለበትም።

# ሶስተኛው ማዕዘን

## *ዘካ መስጠት*

ዘካ፣ አላሁ ﷻ ሀብታሞች ከገንዘባቸው ቀንሰው ለድሆች እንዲሰጡ ግዴታ ያደረገው ህግ ነው፤

﴿وَٱلَّذِينَ فِىٓ أَمۡوَٰلِهِمۡ حَقٌّ مَّعۡلُومٌ ﴿٢٤﴾ لِّلسَّآئِلِ وَٱلۡمَحۡرُومِ ﴿٢٥﴾﴾ المعارج: ٢٤ - ٢٥

**« እነዚያ፤ ለለማኝ እን ከልመና ለሚቆጠቡ በገንዘቦቻቸው ላይ የታወቀ መብት ያለባቸው የኾኑት።»** (መዓሪጅ፣ 24-25)

የዘካ ህግ በሱናነት ወይም በሙስተሀብነት (የተወደደ) ወይም በበጎ አድራጎት (ተበሩዕ) የሚፈፀም ሳይሆን ግዴታ ነው - በአላህ ለድሆች የተደነገገ ሀቅ። ነፍሱ ወዳና ፈቅዳ ግዴታ የሆነበትን ዘካ የሰጠ ሰው ስራው ተቀባይነት ይኖረዋል። የዘካን ዋጅብነት

[6] ኢብን ማጃህ ዘግበውታል

በመቃወም የከለከለ ሰው ከሀዲ (ካፊር) ይሆናል:: ነገር ግን የዘካን ዋጅብነት አምኖ፣ በንፉግነት «እምቢ፣ አልሰጥም» ካለ፣ ኢስላማዊ መንግስት ባለበት አገር የሙስሊሞች መሪ ከቅጣት ጋር በሀይል ሊቀበለው ይገባል:: እምቢተኛው ሰው ጦር ያደራጀ ከሆነም፣ የሙስሊሞች መንግስት ያገሪቱን የጦር ሀይል በማዝመት መዋጋት አለበት፤ልክ አቡበክር ከነብዩﷺ በኋላ «ዘካ አንሰጥም» በማለት በአመፁ ሰዎች ላይ እንደ ዘመቱት ሁሉ::

## አራተኛው ማዕዘን

### *የረመዷንን ወር መፆም*

አላህ እንዲህ ይላል:-

﴿شَهۡرُ رَمَضَانَ ٱلَّذِيٓ أُنزِلَ فِيهِ ٱلۡقُرۡءَانُ هُدٗى لِّلنَّاسِ وَبَيِّنَٰتٖ مِّنَ ٱلۡهُدَىٰ وَٱلۡفُرۡقَانِۚ فَمَن شَهِدَ مِنكُمُ ٱلشَّهۡرَ فَلۡيَصُمۡهُۖ ١٨٥﴾ البقرة: ١٨٥

***«የረመዳን ወር ያ፤ በርሱ ውስጥ ቁርኣን ለሰዎች መሪ፣ ከቅን መንገድና እውነትን ከውሸት ከሚለዩም ገላጭ አንቀጾች ሲኾን የተወረደበት ነው:: ከእናንተም ወሩን ያገኘ ሰው ይጹመው::»*** *(በቀራህ፣185)*

አንድ ሙስሊም ጤናማ ከሆነና በሚኖርበት አገር ካለ የረመዷን ወር እንደ ገባ መፆም አለበት:: ነገር ግን ሸሪዓዊ ምክንያት ካለው አፍጥሮ በሌላ ጊዜ ያፈጠረውን ቀን ያህል ቆጥሮ መፆም ግዴታው ነው::

﴿فَمَن شَهِدَ مِنكُمُ ٱلشَّهۡرَ فَلۡيَصُمۡهُۖ وَمَن كَانَ مَرِيضًا أَوۡ عَلَىٰ سَفَرٖ فَعِدَّةٞ مِّنۡ أَيَّامٍ أُخَرَۗ﴾ البقرة: ١٨٥

***«... ከናንተም ወሩን ያገኘ ይጹመው፤ በሽተኛ ወይም በጉዞ ላይ የኾነም ሰው ከሌሎች ቀኖች በልኩ መጾም አለበት...»*** *(በቀራህ፣185)*

በሌላ በኩል በእርጅና ምክንያት መፆም ያልቻለ ሰው በየቀኑ ምስኪን መመገብ ይኖርበታል፤

﴿وَعَلَى ٱلَّذِينَ يُطِيقُونَهُۥ فِدۡيَةٞ طَعَامُ مِسۡكِينٖۖ﴾ البقرة: ١٨٤

*«..በነዚያም ጾምን በማይችሉት ላይ ቤዛ ድኻን ማብላት አለባቸው...» (በቀራህ፣184)*

## አምስተኛው ማዕዘን

### *አቅም ላለው ሰው ሀጅ ማድረግ*

«ሀጅ» በቋንቋው ትርጉሙ «ቀስድ» ማለትም «ማሰብ ወይም ማለም» ማለት ነው:: በሸሪአዊ ትርጓሜው ደግሞ በተከበረው የአላህ ቤትና በዙሪያዎቹ በሚገኙ የሀጅ ስርአት መፈፀሚያ ቦታዎች ወደ አላህ ለመቃረብ አስቦ የሀጅንም ይሁን የኡምራን የአምልኮ ስርዓት ማሰብና መፈፀም ማለት ነው::

አንድ ሙስሊም ከመካ ውጭ ሀጅ ቢፈፅም ሀጁ ተቀባይነት የለውም:: «ወደ ዶሪህ፣ ቀብር ወይም አምልኮት ወደሚፈፀምበት ዛፍ ሄዶ ሀጅ መፈፀም ይቻላል» የሚል እምነት ካለው ደግሞ፣ በቀጥታ ከኢስላም ጎዳና ይወጣል:: የሀጅ ስርዓት የሚፈፀመው በተወሰነ ጊዜ ነው፤

﴿ٱلْحَجُّ أَشْهُرٌ مَّعْلُومَٰتٌ﴾ البقرة: ١٩٧

*«ሐጅ (ጊዜያቱ) የታወቁ ወሮች ናቸው...»*

ኡምራ የሚፈጸምበት የተደነገገ ልዩ ወቅት የለውም፤ በአመት ውስጥ በማንኛውም ወቅት ሊፈጸም ይችላል::

﴿وَلِلَّهِ عَلَى ٱلنَّاسِ حِجُّ ٱلْبَيْتِ مَنِ ٱسْتَطَاعَ إِلَيْهِ سَبِيلًا﴾ آل عمران: ٩٧

***«...ለአላህም በሰዎች ላይ ወደርሱ (መስጅደል ሀረም) መኼድን በቻለ ሁሉ ላይ ቤቱን የመጎብኘት ግዴታ አለባቸው...»***

ወደ መካ ሄዶ ሀጅ ማድረግ ከፍተኛ የሆነ የትራንስፖርት፣ የማረፊያ ቦታና የምግብ ወጭ የሚጠይቅ በመሆኑ፣ አላህ ግዴታነቱን ከአካላዊና ከኢኮኖሚያዊ አቅም ጋር አያይዞ ነው የደነገገው:: አንድ ሰው አካላዊ አቅም ወይም ችሎታ ኖሮት፣ የገንዘብ አቅም ከሌለው ወይም የገንዘብ አቅም ኖሮት በአካሉ ደካማ ወይም ህመምተኛ ከሆነ ሀጅ የማድረግ ግዴታ አይኖርበትም:: ሆኖም ሀጅ ለማድረግ የሚያስችል ገንዘብ

እስካለው ድረስ ግን፣ወጪውን ሸፍኖ ሌላን ሰው በመላክ ሀጁን በውክልና ማስደረግ ይኖርበታል።

የሀጅ ስርዓት ሰዎች ረጅም ጉዞ በማድረግ ከአራቱም የአለም ማዕዘናት ወደ መካ በመሄድ የሚፈፅሙት አምልኮ በመሆኑ፣ አስቸጋሪና ፈታኝ ነው፤ ቀላል የማይባል ጊዜ፣ ጉልበትና ፅናትን ይጠይቃልና። ስለሆነም ደጋግሞ ሀጅ ለማድረግ አቅም ባላቸው ሰዎች ላይ ጭምር፣ በህይወት ዘመን አንድ ጊዜ ብቻ መፈፀም ግዴታዊ የአምልኮ ተግባር ተደርጓል። ይህ ደግሞ አላህ ለሰዎች ካለው እዝነት ነው።

عن أبو هريرة – رضي الله عنه – : قال : خَطبَنا رسولُ الله –صلى الله عليه وسلم– فقال : «يا أيها الناسُ ، قد فُرِضَ عليكُم الحجُّ ، فَحُجُّوا ، فقال رجل : أفي كُلِّ عامٍ يا رسول الله ؟ فَسَكَتَ حتى قالها ثَلاثا ، ثم قال : ذروني ما تركتُكم ، ولو قلتُ: نَعمْ لوَجَبتْ ، وَلَمَا اسْتَطَعتُم، وَإِنَّمَا أهْلَكَ مَن كانَ قَبلَكم كَثرَةُ سُؤالِهِمْ ، واختلافُهُمْ على أنبيائهم ، فإذا أمَرْتُكُمْ بشيءٍ فائتُوا منه ما اسْتَطَعْتُمْ ، وإذا نهيتُكُمْ عن شيء فاجتنبوه». أخرجه مسلم

አቡ ሁረይራ ባስተላለፉት ሀዲስ ነብዩﷺ፤ (*‹‹እናንተ ሰዎች ሆይ! አላህ ሀጅን ግዴታ አድርጎባችኋልና፤ ሀጅ አድርጉ››* በማለት ሲናገሩ፣ አንድ ሰው *‹‹በያመቱ ነው ሀጅ የምናደርገው ያ ረሱለላህ?››* በማለት ጠየቀ። ሰውየው ጥያቄውን ሶስት ጊዜ ደጋግሞ እስከሚጠይቅ ረሱል ዝም አሉ። ከዚያም እንዲህ በማለት መልስ ሰጡ፤ **‹‹‘አዎን’ ብዬህ ቢሆን ኖሮ፣ በእናንተ ላይ ግዴታ በሆነና እናንተም መፈፀም ባልቻላችሁ ነበር። ከእናንተ በፊት የነበር ህዝቦችን ያጠፋቸው አግባብ ያልህኑ ጥያቄውችን ማብዛታቸው እን ስለ ነብዮቻቸው መወዝገባቸው ነበር። አንድን ነገር ካዘዝኳችሁ የቻላችሁትን ያህል ለመተግበር ምክሩ፣ አንድን ነገር ከከለከልኳችሁ ግን ተቆጠቡ››** አሉት።) *ሙስሊም* **ዘግበዉታል**

ምስጋና ለአላህ ይገባውና የሀጅ ግዴታነቱ በህይወት ዘመን አንድ ጊዜ ብቻ ነው። ሆኖም አንድ ሰው ግዴታ የተደረገበትን ሀጅ ከፈፀመ በኋላ፣ አንዴም ሆነ ከዚያ በላይ በድጋሚ የሚፈፅመው ሀጅ በትርፍ ይያዝለታል።

# ሁለተኛው የጅብሪል ጥያቄ

## «ስለኢማን ይንገሩኝ?»

ጅብሪል ስለኢስላም ከረሱል ﷺ በቂ ማብራሪያ ካገኙ በኋላ፣ በመቀጠል ያቀረበላቸው ጥያቄ *‹‹ስለኢማን ይንገሩኝ?››* የሚል ነው:: ***«ኢማን (እምነት) ማለት በአላህ በመላእክቶቹ፣ በመጻህፍቱ፣ በመልዕክተኞቹ፣ በመጨረሻው ቀን እንዲሁም ጥሩም ይሁን መጥፎ በአላህ ውሳኔና ፍቃድ (ቀደር) እንደሚከሰት ማመን ነው»*** ብለው ነብዩ ﷺ መለሱለት::

በቋንቋ ደረጃ «***ኢማን***» ማለት «ጥርጣሬ ያልገባበት ቁርጠኛ እምነት» ማለት ነው:: ሸሪአዊ ትርጉሙ ደግሞ በልብ ማመንን፣ በምላስ መናገርንና በአካል መተግበርን የሚያካትት ነው:: «***ኢማን***» አላህን በመታዘዝ ሲጨምር፣ ወንጀል በመስራት ደግሞ ይቀንሳል:: ይህ የአህሉሱና ትክክለኛ አመለካከት ነው::

«አንዱን ጥሎ፣ አንዱን አንጠልጥሎ» እንዲሉ፣ ሙርጂዓዎች (ስራ ከእምነት አይቆጠርም የሚነጥሉ ቡድኖች) «***ኢማን*** ***ማለት*** በልብ ብቻ ማመን ነው» ወይም ደግሞ «በልብ ታምኖበት በምላስ የሚነገር ብቻ ነው» በማለት፣ ከአህሉሱና ትክክለኛ ግንዛቤ ተቃራኒ የሆነና የተሳሳተ ትርጓሜ ይሰጣሉ:: እነዚህ ቡድኖች «ተግባር ከኢማን አይገባም» ባዮች ናቸው:: ሆኖም ይህ አባባላቸው ፍፁም ስህተት ነው፤ተግባር ከኢማን ይካተታልና:: ያለተግባር አንድ ሰው «ሙዕሚን» ሊባል አይችልም:: «ለምን?» ቢባል፣ አላህ እምነትን ከተግባር ጋር አጣምሮ ተናግሯልና፤

﴿إِنَّمَا ٱلۡمُؤۡمِنُونَ ٱلَّذِينَ إِذَا ذُكِرَ ٱللَّهُ وَجِلَتۡ قُلُوبُهُمۡ وَإِذَا تُلِيَتۡ عَلَيۡهِمۡ ءَايَٰتُهُۥ زَادَتۡهُمۡ إِيمَٰنٗا وَعَلَىٰ رَبِّهِمۡ يَتَوَكَّلُونَ ٢ ٱلَّذِينَ يُقِيمُونَ ٱلصَّلَوٰةَ وَمِمَّا رَزَقۡنَٰهُمۡ يُنفِقُونَ ٣ أُوْلَٰٓئِكَ هُمُ ٱلۡمُؤۡمِنُونَ حَقّٗاۚ لَّهُمۡ دَرَجَٰتٌ عِندَ رَبِّهِمۡ وَمَغۡفِرَةٞ وَرِزۡقٞ كَرِيمٞ ٤﴾ الأنفال: ٢ - ٤

***«ፍጹም ምእመናን የሚባሉት እነዚያ አላህ በተወሳ ጊዜ ልቦቻቸው የሚፈሩት፣ በነሱም ላይ አንቀጾቻችን በተነበቡ ጊዜ***

***እምነትን የሚጨምሩላቸው፣ በጌታቸውም ላይ ብቻ የሚመኩት ናቸው፤ እነዚያ ሶላትን ደንቡን አሟልተው የሚሰግዱ፣ ከሰጠናቸውም ሲሳይ የሚለግሱ ናቸው፤ እነዚያ በውነት አማኞች እነሱ ብቻ ናቸው።» (አንፋል፣ 2-4)***

﴿إِنَّمَا ٱلۡمُؤۡمِنُونَ ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ بِٱللَّهِ وَرَسُولِهِۦ ثُمَّ لَمۡ يَرۡتَابُواْ وَجَٰهَدُواْ بِأَمۡوَٰلِهِمۡ وَأَنفُسِهِمۡ فِي سَبِيلِ ٱللَّهِۚ أُوْلَٰٓئِكَ هُمُ ٱلصَّٰدِقُونَ ١٥﴾ الحجرات: ١٥

***«(እውነተኛዎቹ) ምእመናን እነዚያ በአላህና በመልክተኛው ያመኑት፣ ከዚያም ያልተጠራጠሩት በገንዘቦቻቸውና በነፍሶቻቸውም በአላህ መንገድ የታገሉት ብቻ ናቸው፤ እነዚያ እነሱ እውነተኞቹ ናቸው።» (ሁጁራት፣ 15)***

ነብያችን በሀዲሳቸው እንዲህ ይላሉ፤

عن أبي هريرة رضي الله عنه عن النبي ﷺ قال: «الإِيمَانُ بِضْعٌ وَسَبْعُونَ أَوْ بِضْعٌ وَسِتُّونَ شُعْبَةً فَأَفْضَلُهَا قَوْلُ لاَ إِلَهَ إِلاَّ اللَّهُ وَأَدْنَاهَا إِمَاطَةُ الأَذَى عَنِ الطَّرِيقِ وَالْحَيَاءُ شُعْبَةٌ مِنَ الإِيمَانِ» رواه البخاري ومسلم

***«ኢማን ከ73-79 ወይም ከ63-69 ቅርንጫፎች አሉት። በላጩ 'ላኢላሀ ኢለላህ' የሚለው ንግግር ሲሆን፣ ዝቅተኛው ደግሞ እንቅፋት ሊሆን የሚችልን ነገር ከመንገድ ማስወገድ ነው። ሀያዕም[7] (ትህትና) ከኢማን ቅርንጫፎች አንዱ ነው።»*** [8] ይህ ሀዲስ የሚያመላክተው ኢማን ልባዊ እምነት፣ ንግግር፣ ወይም ተግባር ብቻ ሳይሆን፡ የሶስቱም ማለትም ጥምር ውጤት መሆኑን ነው። በሀዲሱ ውስጥ ***«በላጩ ላኢላሀ ኢለላህ»*** በማለት የተገለፀው ቃል፣ በአንደበት የመናገርን አስፈላጊነት ያመላክታል። «***እንቅፋት ሊሆን የሚችልን ነገር ከመንገድ ማስወገድ***» የሚለው ቃል ደግሞ የተግባርን አስፈላጊነት ያመላክታል። «***ሀያዕም (ትህትና) ከኢማን ቅርንጫፎች አንዱ ነው***» የሚለው ደግሞ

---

[7] «ሀያዕ» የሚለው የአረብኛ ቃል በሸሪአዊ ትርጉሙ፣ አንድ ሰው አላህ ያዘዘውን መልካም ስራ እንዲሰራ፣ የከለከለውን መጥፎ ተግባር እንዲርቅ የሚያስገድድ ውስጣዊ ስሜትና ግፊት ማለት ነው። «ትህትና» የሚለውን ቃል የተጠቀምኩት ከዚህ ውጭ ሊተካው የሚችል ሌላ ቃል ስላላገኘው ነው።

[8] ቡኻሪና ሙስሊም ዘግበዉታል

የልብ ስራን ያመላክታል። ይህ ሀዲስ «*ኢማን*» የነዚህ ሶስት ነገሮች ማለትም የንግግር፣ የልብ እምነትና የተግባር ጥምር ውጤት መሆኑን ይጠቁማል።

ስለሆነም አቅም እያለው ስራን ወይም ተግባርን ከነአካቴው አውቆ የተወ ሰው «ሙስሊም» ወይም «ሙእሚን» አይባልም። ከኢስላም ተግባራት ውስጥ የተወሰነውን የተወ፣ የእምነት ጉድለት ይኖርበታል፤ ወይም ከከሀዲ ሊፈረጅ ይችላል። ለምሳሌ አንድ ሰው ሶላትን ሆን ብሎም ይሁን በቸልተኝነት ከነአካቴው ከተወ፣ የአብዛኛው የአህሉሱና አቋም «ከኢስላም ጎዳና ይወጣል» የሚል ነው። ከሶላትና ከሸሀደተይን (ላኢላሀ ኢለላህ፣ ሙሀመድ ረሱሉላህ) ውጭ ካሉ ተግባራት መካከል አንዱን የአምልኮ ተግባር ግዴታነት ተቀብሎ ሳይፈፅም ቢቀር፣ እምነቱ ጎደሎ ይሆናል። ስለሆነም ከሽርክ በታች ያሉ ወንጀሎችን ለፈጸመ ግለሰብ የሚሰጠው አይነት ብይን ይሰጠዋል።

በመሆኑም ኢስላምንና ኢማንን ማጣመር ግድ ነው፤ትክክለኛ ኢማን የሁለቱ ድምር ውጤት ነው። አንድ ሰው በኢስላም ላይ ብቻ ተወስኖ፣ ኢማንን ከተወ ከሙናፊቆች ይፈረጃል። ይህ ሁኔታ ከዚህ በፊት እንደተገለፀው በረሱል ﷺ ዘመን በነበሩ ሙናፊቆች ላይ ይታይ የነበረ ሀቅ ነው። ውጫቸው ሰልሞ ውስጣቸው ግን አልተቀበለውም ነበር። ለምሳሌ ይሰግዳሉ፤ ይፆማሉ፤ ጅሀድ ይወጣሉ፤ ወዘተ.. ነገር ግን እየሰሩት ያለውን ተግባር በውስጣቸው አያምኑበትም ነበር። ለዚህም ነው አላህ ከመጨረሻው የእሳት አዘቅት ውስጥ ለዘላለሙ ሊዘፍቃቸው ቀጠሮ የያዘላቸው፣ የማይሻር የከፋ ቀጠሮ።

በአንፃሩ አንድ ሰው ውስጡ ተቀብሎ፣ በይፋ ካልመሰከረና ካልተገበረ «ሙስሊም» አይባልም። የመካ ሙሽሪኮች፣ አይሁዶችና ነሷራዎች የሙሀመድን ትክክለኛ መልዕክተኛነት በልባቸው ያውቁት ነበር። ነገር ግን ይህን በይፋ ተናገሩ ወይም መስክሩ በተባሉ ጊዜ አልመሰከሩም። አላህ እንዲህ ይላል፤

﴿قَدۡ نَعۡلَمُ إِنَّهُۥ لَيَحۡزُنُكَ ٱلَّذِي يَقُولُونَۖ فَإِنَّهُمۡ لَا يُكَذِّبُونَكَ وَلَٰكِنَّ ٱلظَّٰلِمِينَ بِـَٔايَٰتِ ٱللَّهِ يَجۡحَدُونَ ٣٣﴾ الأنعام: ٣٣

***«እነሆ ያ የሚሉህ ነገር እንደሚያሳዝንህ በእርግጥ እናውቃለን፤ እነርሱም (በልቦቻቸው) አያስተባብሉህም፤ ግን በዳዮቹ በአላህ አንቀጾች ይክዳሉ።»*** *(አንዓም፣ 33)*

የነብዩ አጎት -አቡጧሊብ- በበኩሉ ተከታዩን ገጥሟል ወደ አማርኛም እንዲህ መልሰነዋል፡-

وعرضت ديناً قد عرفت بأنّه ... من خير أديان البرية ديناً

لولا الملامة أو حِذار مسبّة ... لوجدتني سمحاً بذاك مبيناً

**«አውቂያለሁ ያቀረብከዉን ሀይማኖት**
**መላቅ፣ መብለጡን ከሁሉም እምነት፣**
**ወቀሳና ስድብ ባልፈራ**
**ለክብር ለዝናዬ ባልራራ**
**ማን ነበር ከኔ ቀድሞ የሚመሰክር**
**የኢስላምን ታላቅነት፣ የኢስላምን ክብር።»**

አቡጧሊብን «ላኢላሀ ኢለላህ፣ ሙሀመድ ﷺ ረሱሉላህ» የሚለውን የምስክርነት ቃል ከመናገር ያገደው ከህብረተሰቡ ጋር የነበርው የጠበቀ የማህበራዊ ህይወት ትስስር መሆኑ ግልጽ ነው። በልቡ የመሰከረውንና በግጥም የገለፀውን ያህል በአንደበቱ «ላኢላሀ ኢለላህ፣ ሙሀመዱ ረሱሉላህ» ቢል ኖሮ፣የአካባቢው ማህበረሰብ ከሚከተለው እምነት ባገለለ ነበር። ተስፋ ያልቆረጡት ነብዩ ﷺ «እስልምናን ሊቀበል ይችላል» በማለት፣ ሊሞት በተቃረበበት ወቅት ጭምር ‹‹***አጎቴ ሆይ! ላኢላሀ ኢለላሀ በል***›› በማለት ተማጽነውታል። የሞት አፋፍ ላይ ባለበት በዚህ ወቅት 'የክፉ ጓደኛ ምክሩም ክፉ ነውና' የአቡጧሊብ የቅርብ ጓደኛ የሆነው አቡጀህል በበኩሉ፣ ‹‹***የአብዱል ሙጦሊብን ሀይማኖት ትተዋለህን?***›› በማለት ወትውተውታል። እናም አቡጧሊብ ‹‹***እርሱ በአብዱል ሙጦሊብ ሀይማኖት ላይ መሆኑን ገልጾ***››

ሞተ፤ እናም ይህች የክህደት ቃል የመጨረሻ ቃሉ ሆነች። በልቡ እየመሰከረ ነገር ግን በአንደበቱ «ላኢላሀ ኢለላህ» ባለማለቱ የእሳት ሆነ።

አቡጧሊብ የኢስላምን ትክክለኛነት ያለ ጥርጥር አውቋል። ከዚህም በተጨማሪ ላኢላሀ ኢለላህን በአንደበታቸው እያሉ፣ ትርጉሙን በውል እንደማይረዱት የዘመናችን በርካታ ሙስሊሞች ሳይሆን፣ የቃሉን ትክክለኛ ትርጓሜ ጠንቅቆ ተረድቶታል። «ላኢላሀ ኢለላህ» ብሎ መመስከር ማለት፣ ያለበትን ማህበረሰብ እምነት አውልቆ መጣል መሆኑን በሚገባ አውቋል። «ታዲያ ከፊቱ የቀረበለትን ሀቅ ከመቀበል ምን አገደው?» ከተባለ፣ መልሱ «ጃሂልያ» (ድንቁርና፤መሀይምነት) ነው። የጃሂልያ ወገንተኝነትና እልህ ወደ ክህደት (ኩፍር) ይገፋፉል። አላህ እንዲህ ይላል፡-

﴿إِذْ جَعَلَ ٱلَّذِينَ كَفَرُوا۟ فِى قُلُوبِهِمُ ٱلْحَمِيَّةَ حَمِيَّةَ ٱلْجَٰهِلِيَّةِ فَأَنزَلَ ٱللَّهُ سَكِينَتَهُۥ عَلَىٰ رَسُولِهِۦ وَعَلَى ٱلْمُؤْمِنِينَ وَأَلْزَمَهُمْ كَلِمَةَ ٱلتَّقْوَىٰ وَكَانُوٓا۟ أَحَقَّ بِهَا وَأَهْلَهَا ۚ وَكَانَ ٱللَّهُ بِكُلِّ شَىْءٍ عَلِيمًا ٢٦﴾ الفتح:٢٦

***«እነዚያ የካዱት የመሀይምነቱን (የጃሂሊያ) እልህ በልቦቻቸው ውስጥ ባደረጉ ጊዜ (በቀጣናቸው ነበር)፤ አላህም በመልክተኛው ላይና በምእመናኖቹ ላይ እርጋታውን አወረደ...» (ፈትህ፣ 26)***

ከላይ ሲል የቀረበው ማብራሪያ የኢማንን ምንነት የሚያስረዳ ነው። ኢማን በስድስት ማዕዘናት ማለትም በአላህ፣ በመላኢካዎቹ፣ በመፃህፍቱ፣ በመልእክተኞቹና በመጨረሻው ቀን እንዲሁም መልካምም ይሁን መጥፎ በአላህ ውሳኔ የሚከናወን መሆኑን በማመን ላይ የተገነባ ነው። የእነዚህ ማዕዘናት ዝርዝር ማብራሪያቸው በሚከተለው መንገድ ቀርቧል።

## የመጀመሪያው ማዕዘን

### *በአላህ ማመን*

«በአላህ ማመን» ማለት፣ አላህ ብቸኛና ተጋሪ የሌለው፣ አምልኮት የሚገባው፣ መልካም የሆኑ ስሞችና ደጋግ ባህሪያት

ያሉት መሆኑን ማመን ነው:: በአላህ ማመን ሶስት ዓይነት የተውሂድ ክፍሎችን ያካትታል፤ **ተውሂደ አል-ሩቡቢያ** (አላህን በጌትነቱ ብቸኛ ማድረግ)፣ **ተውሂደል ኡሉህያ** (አላህን በአምልኮ ብቸኛ ማድረግ) **እና ተውሂዱል አስማኢ ወሲፋት** (አላህን በስሞቹና በባህርያቱ ብቸኛ ማድረግ):: አንድ ሰው ሙዕሚንነቱ ሊረጋገጥ የሚችለው በእነዚህ ሶስት የተውሂድ ክፍሎች ሙሉ በሙሉ ሲያምን ነው:: አንዳንድ ሰዎች «አንድ ሙስሊም የአላህን መኖር ብቻ ካመነ ሙዕሚን ነው» ይላሉ:: ይህ እጅግ የተሳሳተ አመለካከት ነው::እምኘነት በሶስቱም የተውሂድ ክፍሎች ማመንን ይጠይቃል:: ከነዚህ አንዱ ከጎደለ፣ «በአላህ አምኗል» ሊባል አይችልም::

**ተውሂደ አል-ሩቡቢያ (በአላህብቸኛ ጌትነት ማመን)-** ማለት አላህ፤ በመፍጠር፣ በማስተናበር፣ ፍጡራን በህይወት ለመኖር የሚያስፈልጋቸውን ነገር ሁሉ በማዘጋጀትና በመለገስ፣ ህይወት በመስጠትና በመንፈግ ጭምር ብቸኛ አምላክ መሆኑን ማመን ማለት ነው:: ይህንን የእምነት ክፍል በምድር ላይ የሚያስተባብሉ ሰዎች በጣም ጥቂት ናቸው:: ሙእሚኑም፣ ከሀዲውም የሩቡቢያን የእምነት ክፍል አረጋጋጭ ነው:: ለዚህም ማስረጃው ይሄ ነው:: አላህ እንዲህ ይላል፤

﴿وَلَئِن سَأَلْتَهُم مَّنْ خَلَقَهُمْ لَيَقُولُنَّ ٱللَّهُ فَأَنَّىٰ يُؤْفَكُونَ ﴿٨٧﴾﴾ الزخرف: ٨٧

***«ማን እንደፈጠራቸውም ብትጠይቃቸው በእርግጥ 'አላህ ነው' ይላሉ:: ታዲያ (ከእምነት) ወዴት ይዞራሉ::»*** *(ዙኹሩፍ፣ 87)*

﴿قُل لِّمَنِ ٱلْأَرْضُ وَمَن فِيهَآ إِن كُنتُمْ تَعْلَمُونَ ﴿٨٤﴾ سَيَقُولُونَ لِلَّهِ ۚ قُلْ أَفَلَا تَذَكَّرُونَ ﴿٨٥﴾﴾ المؤمنون: ٨٤ - ٨٥

***«ምድርና በውስጥዋ ያለው ሁሉ የማን ነው? 'የምታውቁ ብትኾኑ (ንገሩኝ)' በላቸው:: በእርግጥ 'የአላህ ነው' ይሉሃል፤ 'ታዲያ አትገሰጹም?' በላቸው::»*** *(ሙእሚኑን 84-85)*

﴿قُلْ مَن يَرْزُقُكُم مِّنَ ٱلسَّمَآءِ وَٱلْأَرْضِ أَمَّن يَمْلِكُ ٱلسَّمْعَ وَٱلْأَبْصَٰرَ وَمَن يُخْرِجُ ٱلْحَىَّ مِنَ ٱلْمَيِّتِ وَيُخْرِجُ ٱلْمَيِّتَ مِنَ ٱلْحَىِّ وَمَن يُدَبِّرُ ٱلْأَمْرَ ۚ فَسَيَقُولُونَ ٱللَّهُ ۚ فَقُلْ أَفَلَا تَتَّقُونَ ﴿٣١﴾﴾ يونس: ٣١

***«'ከሰማይና ከምድር ሲሳይን የሚሰጣችሁ ማን ነው? መስሚያዎችንና ማያዎችንስ የፈጠረ ማን ነው? ከሙትም ሕያውን የሚያወጣ፣ ከሕያውም ሙትን የሚያወጣስ ማን ነው? ነገሩን ሁሉ የሚያስተናብርስ ማን ነው?' በላቸው፤ በእርግጥ 'አላህ ነው' ይሉሀል፡፡ 'ታዲያ (ለምን ታጋራላችሁ?) አትፈሩትምን?' በላቸው፡፡» (ዩኑስ፣ 31)***

ሰዎች በተውሂደል ሩቡቢያ ቢያምኑም፣ በተውሂደል ኡሉህያ ካላመኑ እምነታቸው ተቀባይነት ሊኖረው አይችልም፡፡

**ተውሂደል ኡሉህያ (አላህን በአምልኮ ብቸኛ ማድረግ) -** ማለት አምልኮትን ሙሉ በሙሉ ለአላህ ብቻ ማድረግ ማለት ነው፡፡ ከአላህ በተላኩ ነብያትና በህዝቦቻቸው መካከል ከፍተኛ እሰጥ-አገባ ከማስነሳት አልፎ ፍጥጫና ግጭትን የፈጠረው ይህ የተውሂድ ክፍል ነበር ተውሂዱል ኡሉህያ፡፡ በመካ የነበሩ ሙሽሪኮች በአላህ ፈጣሪነትና መጋቢነት (ሩቡቢያ) ሙሉ በሙሉ ያምኑ ነበር፡፡ ከኡሉህያ አንጻር ሲመዘኑ ግን፣ ከአላህ ጋር ሌላን አካል ያመልካሉ፤ ለሌላ አካል ይሳላሉ፣ ይሰዋሉ፤ ከአላህ ውጭ ያሉ አካላትን «ድረሱልኝ» በማለት፣ መንፈሳዊ እርዳታን ይማጸናሉ፡፡ ስለሆነም በዘመናችንም ይህን መሰሉን ተግባር የሚፈጽም ሁሉ፣ ልክ እንደ ቁረይሾች ይቅር የማይባል የሽርክ ወንጀል እየፈፀመ መሆኑን ማወቅ አለበት፡፡

**ተውሂዱል አስማኢ ወሲፋት (አላህን በስሞቹና በባህርያቱ ብቸኛ ማድረግ)-** ይህ ማለት፣ አላህ ስለራሱ እንዲሁም ረሱልﷺ ስለአላህ ስለተናገሯቸው መልካም ስሞችና ባህርያት ሌላ ትርጉም ሳይሰጡ፣ ከፍጡራን ጋር ሳያመሳስሉ ወይም ትርጉም አልባ ሳያደርጉ ሙሉ በሙሉ አምኖ መቀበል

ማለት ነው። ረሱል የነበሩበትን ዘመን ጨምሮ ከሶስቱ ወይም ከአራቱ ምርጥ ክፍለ ዘመናት በኋላ ለአላህ መልካም ስሞችና ባህሪያት ሌላ ትርጉም የሚሰጡ፣ ከፍጡራን ጋር የሚያመሳስሉና ትርጉም አልባ የሚያደርጉ ቡድኖች ተፈጥረዋል። ከእነዚህ ቡድኖች መካከል ጀህምያ፣ ሙዕተዚላ፤ አሻኢራህና አህባሽ ይገኙበታል። ከነዚህ ቡድኖች ውስጥ ከፊሎቹ የአላህ ስሞችንና ባህሪያትን የካዱ ናቸው። በሌላ በኩል የአላህን ስሞች አረጋግጠው ባህሪያቱን የካዱም አለ። ሌሎች ቡድኖች በበኩላቸው ከባህሪያቱ መካከል የተወሰኑትን ብቻ አጽድቀዋል።

እነዚህን ቡድኖች አንድ የሚያደርጋቸው ነገር ቢኖር፣ ከአላህ ስሞች ወይም ባህርያት ወይም ከሁለቱም የተወሰኑትን የሚክዱ መሆናቸው ነው። ስለሆነም ጥፋታቸው እኩል ነው። አንድ ሰው በአንዱ የአላህ ስም ወይም ባህሪ ከካደ እንደ አማኝ አይቆጠርም። ከሰለፎች አንዱ እንዲህ ይላል፤ **‹‹የሰለፎች ጎዳና አላህ ስለራሱ፣ ነብዩም ﷺ ስለአላህ የገለጹትን ባህሪ ሳያጣምሙ፣ ትርጉም አልባ ሳያደርጉ፣ ‘እንዴት’ የሚል ጥያቄ ሳያነሱና ከምንም ነገር ጋር ሳያመሳስሉ ማረጋገጥ ነው።››**

# ሁለተኛው ማዕዘን

## *በመላኢኮች ማመን*

«መላኢካ» ማለት «መለክ» ከሚለው ስርወ ቃል የመጣ ሲሆን፣ ትርጉሙም «መልእክተኛ» ማለት ነው። በመላኢካ ማመን ማለት «መላኢካዎች አላህ ከኑር (ብርሀን) የፈጠራቸው፣ የአላህን ትዕዛዝ የማይነቅፉ፣ የተለያየ የስራ ድረሻ ያላቸውና ከሰው ልጅ እይታ ስውር የሆኑ ህያው ሰራዊቶች ናቸው ብሎ ማመን» ማለት ነው። ሙስሊም ከምዕመናን እናት አዒሻ በዘገቡት ሀዲስ የአላህ መልእክተኛ ﷺ እንዲህ ብለዋል፤

عَنْ عَائِشَةَ رَضِيَ اللهُ عَنْهَا قَالَتْ: قَالَ رَسُولُ اللهِ ﷺ "خُلِقَتِ الْمَلَائِكَةُ مِنْ نُورٍ، وَخُلِقَ الْجَانُّ مِنْ مَارِجٍ مِنْ نَارٍ، وَخُلِقَ آدَمُ مِمَّا وُصِفَ لَكُمْ " رَوَاهُ مُسْلِمٌ

***«መላኢካ ከብርሀን ተፈጠረ፤ ጅን ከእሳት ነበልባል ተፈጠረ፤ አደም ለእናንት ከተገለፀላችሁ (ከአፈር) ተፈጠረ::»***

መላኢካዎች የተለያየ ተግባር ያላቸው የአላህ ሰራዊቶች ናቸው:: ለምሳሌ ጅብሪል ለወህይ (የአላህን መልእክት ለሩሱሎች ለማድረስ) የተመደበ ነው:: ሚካኢል ዝናብ ለማውረድና አትክልት ለማብቀል፣ ኢስራፊል በዕለተ ትንሳኤ ቀንድ ለመንፋት የተመደቡ ናቸው:: በተጨማሪም ከመላኢካዎች ውስጥ ነፍስ ለማውጣት የተመደበ አለ፤ በማህጸን ውስጥ ላለ ጽንስ አራት ጉዳዮችን (የእድሜውን መጠን፣ ሲሳዩን፣ በህይወት ዘመኑ የሚሰራውንና እድለኛ ወይም ጠማማ መሆኑን) ለመመዝገብ የተመደበ መላኢካ አለ፤ የሰውን ልጅ የእለት ተእለት ስራ (መልካምም ይሁን መጥፎ) ለመመዝገብ የተመደቡ መላኢካዎችም አሉ:: አላህ እንዲህ ብሏል፡-

﴿كَلَّا بَلْ تُكَذِّبُونَ بِالدِّينِ ﴿٩﴾ وَإِنَّ عَلَيْكُمْ لَحَافِظِينَ ﴿١٠﴾ كِرَامًا كَاتِبِينَ ﴿١١﴾ يَعْلَمُونَ مَا تَفْعَلُونَ ﴿١٢﴾﴾

الانفطار: ٩ - ١٢

*«በናንተ ላይ ተጠባባቂዎች እያሉባችሁ... በእውነቱ በፍርዱ ቀን ታስተባብላላችሁ፤የምትሰሩትን ሁሉ የሚያውቁ...የተከበሩ ጸሐፊዎች የኾኑ (ተጠባባቂዎች)፡» (ኢንፊጧር፣ 9-12)*

መላኢካዎችን እኛ በአይናችን ልናያቸው አንችልም:: ከእኛ የሚጠበቀው መኖራቸውን፣ የተለያዩ የስራ ዘርፎች እንዳላቸውና አላህ ከሰጣቸው የስራ ሀላፊነት ፍፁም የማያፈነግጡ መሆናቸውን በእርግጠኝነት ማመን ብቻ ነው:: ሙዕሚኖች፣ መላኢካን በተመለከተ መጥፎ አመለካከት እንደ ያዙት ቡድኖች መሆን የለባቸውም:: ለምሳሌ አይሁዶች «ጅብሪል ጠላታችን ነው:: ቁርዓንን ከጅብሪል ውጭ ሌላ መላኢካ ቢያወርደው ኖሮ እናምን ነበር» ብለዋል:: አላህﷻ ይህን በተመለከተ እንዲህ ይላል፡-

﴿قُلْ مَن كَانَ عَدُوًّا لِّجِبْرِيلَ فَإِنَّهُۥ نَزَّلَهُۥ عَلَىٰ قَلْبِكَ بِإِذْنِ ٱللَّهِ مُصَدِّقًا لِّمَا بَيْنَ يَدَيْهِ وَهُدًى وَبُشْرَىٰ لِلْمُؤْمِنِينَ ﴿٩٧﴾ مَن كَانَ عَدُوًّا لِّلَّهِ وَمَلَٰٓئِكَتِهِۦ وَرُسُلِهِۦ وَجِبْرِيلَ وَمِيكَىٰلَ فَإِنَّ ٱللَّهَ عَدُوٌّ لِّلْكَٰفِرِينَ ﴿٩٨﴾﴾ البقرة: ٩٧ ـ ٩٨

***«ለጅብሪል ጠላት የኾነ ሰው (በቁጭት ይሙት) በላቸው፤ እርሱ ቁርአኑን ከበፊቱ ለነበሩት መጻህፍት አረጋገጭ፣ ለምእመናን መሪና ብስራት ሲኾን በአላህ ፈቃድ በልብህ ላይ አውርዶታልና:: ለአላህና ለመላእክቱ፣ ለመልክተኞቹም፣ ለጂብሪልና ለሚካኢልም ጠላት የኾነ ሰው አላህ ለእነዚህ ከሀዲዎች ጠላት ነው::»*** *(በቀራህ፣ 97-98)*

በአይሁዶች የክህደት ንግግር ተጽዕኖ ያደረባቸው አንዳንድ ሺዓዎችም በጅብሪል ላይ ጥላቻ አላቸው:: በዚህም የተነሳ ያለ ምንም ሀፍረት፣ *«ከአላህ የተወረደው ቁርዓን መሰጠት የነበረበት ለአልይ ነበር :: ነገር ግን ጅብሪል አደራውን (አማናውን) በልቶ ለሙሀመድ ሰጠ»* ይላሉ:: አንዱ ገጣሚያቸው እንዲህ ይላል::

**«ነው'ንጂ ታማኙ ጅብሪል መክዳቱ**
**ለአንበሳው አልይ አለመስጠቱ::»**

በሌላም በኩል *«መላኢካዎች የአላህ ሴት ልጆች ናቸው»* የሚሉ ወገኖችም አሉ:: አላህ እንዲህ ይላል፡-

﴿ وَجَعَلُوا۟ ٱلْمَلَٰٓئِكَةَ ٱلَّذِينَ هُمْ عِبَٰدُ ٱلرَّحْمَٰنِ إِنَٰثًا ۚ أَشَهِدُوا۟ خَلْقَهُمْ ۚ سَتُكْتَبُ شَهَٰدَتُهُمْ وَيُسْـَٔلُونَ ﴿١٩﴾﴾ الزخرف: ١٩

***«እነሱ የአልረሕማን ባሮች የኾኑትን መላእክትንም፣ ሴቶች አደረጉ:: ሲፈጠሩ ነበሩን? መመስከራቸው በእርግጥ ትጻፋለች፤ ይጠየቃሉም::»*** *(ዙኽሩፍ፣ 19)*

﴿ أَمْ لَهُ ٱلْبَنَٰتُ وَلَكُمُ ٱلْبَنُونَ ﴿٣٩﴾﴾ الطور: ٣٩

***«ወይስ ለርሱ ሴቶች ልጆች አሉትን? ለእናንተም ወንዶች ልጆች አላችሁን?»*** *(ጡር 39)*

እነዚህና መሰል የቁርአን አንቀጾች የሙሽሪኮች አባባል ምን ያህል የተሳሳተ መሆኑን ያስረዳሉ። ይህ እጅግ የተዛባና የተሳሳተ ግምታቸው የእምነታቸውን ከንቱነት የሚያጋልጥ ነው። ነሷራዎች «ኢሳ የአላህ ልጅ ነው» በማለት፣ ለአላህ ወንድ ልጅን እንዳደረጉለት ሁሉ፣ ሙሽሪኮች በበኩላቸው «አላህ ሴት ልጆች አሉት» አሉ። በህይወት ዘመኑ ጋሻና መከታ የሚሆንና የሚጦር ከሞት በኋላ ደግሞ ስሙን ከምድር በላይ የሚያውል ወንድም ሆነ ሴት ልጅ የሚያስፈልገው የሰው ልጅ ብቻ ነው። አላህ ግን ከዚህ ሁሉ የጠራ ጌታ ነው። ሽሪክ የለውም፤ አንድም እሱን የሚመስልም የለም። እርሱ የተብቃቃ፣ ልጅም ሆነ ሌላ የማያስፈልገው ብቸኛ ጌታ ነው።

## ሶስተኛው ማዕዘን

### ከአላህ በተወረዱ መፃህፍት ማመን

አላህ የሰው ልጆችን ወደ ትክክለኛው ጎዳና ለመምራትና ከባጢል (ከውሸት) ጎዳናዎች ለማራቅ የእርሱን ንግግርና ሸሪዓዎች፣ ትእዛዛትንና ክልከላዎችን ያቀፉ መጽሀፎችን ለነብያት ማውረዱን ማመን ሶስተኛው የኢማን ማዕዘን ነው። አላህ ወደ ነብያት ያወረዳቸው መጽሀፍት እጅግ በርካታ ሲሆኑ፣ ቁጥራቸውን ከአላህ በስተቀር የሚያውቅ የለም። ከነዚህ መፃህፍት መካከል የተወሰኑት ብቻ በቁርአን ተገልፀውልናል፤ እነሱም ሱሁፍ (ለነቢዩ ኢብራሂምና ሙሳ عليه السلام)፣ ተውራት (ለነቢዩ ሙሳ عليه السلام)፣ ዘቡር (ለነቢዩ ዳውድ عليه السلام)፣ ኢንጅል (ለነቢዩ ኢሳ عليه السلام) እና ቁርአን (ለነቢዩ ሙሀመድ ﷺ) ናቸው። አላህ በቁርአኑ እነዚህንና በስም ያልተጠቀሱ ሌሎች መፃህፍት ማውረዱን ስለገለፀ፣ ለማንኛውም ሙስሊም አላህ በቁርዓኑ በስም የገለጸውንም ሆነ ያልገለጸውን አምኖ መቀበል ይኖርበታል። ከአላህ ከወረዱት መፃህፍት ሁሉ በደረጃ ትልቁ ቁርአን መሆኑንም ማመን ያስፈልጋል።

# አራተኛው ማዕዘን

## በመልዕክተኞች ማመን

ከመጀመሪያ እስከ መጨረሻ በተላኩት የአላህ መልዕክተኞች ሁሉ -ስማቸው በቁርዓን በተገለጸውም ሆነ ባልተገለጸው- ማመን ማለት ነው:: አንድ ሰው በሌሎች ነብያት አምኖ በአንዱ ነብይ ብቻ ቢክድ ሁሉንም ነብያት እንደ ካደ ይቆጠራል:: ለምሳሌ አይሁዶች በሁሉም ነብያት አምነው የሙሀመድን ﷺ እና የኢሳን ነብይነት ካዱ:: እንደዚሁ ክርስቲያኖች በሁሉም ነብያት አምነው የሙሀመድን ﷺ ነብይነት እንደ ካዱት ማለት ነው:: አላህ በከፊል አምኖ በከፊል የሚክድን ሰው ስራ አይቀበልም:: አላህ እንዲህ ይላል:-

﴿إِنَّ ٱلَّذِينَ يَكۡفُرُونَ بِٱللَّهِ وَرُسُلِهِۦ وَيُرِيدُونَ أَن يُفَرِّقُواْ بَيۡنَ ٱللَّهِ وَرُسُلِهِۦ وَيَقُولُونَ نُؤۡمِنُ بِبَعۡضٖ وَنَكۡفُرُ بِبَعۡضٖ وَيُرِيدُونَ أَن يَتَّخِذُواْ بَيۡنَ ذَٰلِكَ سَبِيلًا ﴿١٥٠﴾ أُوْلَٰٓئِكَ هُمُ ٱلۡكَٰفِرُونَ حَقّٗاۚ وَأَعۡتَدۡنَا لِلۡكَٰفِرِينَ عَذَابٗا مُّهِينٗا ﴿١٥١﴾﴾ النساء: ١٥٠ - ١٥١

*«እነዚያ በአላህና በመልእክተኞቹ የሚክዱ፣ በአላህና በመልእክተኞቹም መካከል መለየትን የሚፈልጉ... እነዚያ በእውነት ከሀዲዎቹ እነርሱ ናቸው::» (ኒሳእ፣ 150-151)*

በምድራችን ላይ የመጀመሪያው ነብይ አደም ؑ፣ የመጀመሪያው መልእክተኛ (ረሱል) ደግሞ ኑህ ؑ ሲሆኑ፣ የመጨረሻው ረሱል ሙሀመድ ﷺ ናቸው:: አላህ እንዲህ ይላል:-

﴿إِنَّآ أَوۡحَيۡنَآ إِلَيۡكَ كَمَآ أَوۡحَيۡنَآ إِلَىٰ نُوحٖ وَٱلنَّبِيِّـۧنَ مِنۢ بَعۡدِهِۦۚ﴾ النساء: ١٦٣

*«እኛ ወደ ኑህና ከርሱ በኋላ ወደ ነበሩት ነብያት እንዳወረድን ወደ አንተም አወረድን...» (ኒሳእ፣ 163)*

በዘመናችን ያለ ማንኛውም ሙስሊም ካለንበት ዘመን ውጭ የነበሩ ሁሉም ሩሱሎችና ነብያት የሰውን ልጅ ከክህደት ጎዳና ለመታደግ ከአላህ የተላኩ መሆናቸውን በጥቅል ማመን ያለበት

ሲሆን፣ ነብዩ ሙሀመድﷺ በመጡበት ጉዳይ ላይ ግን በዝርዝር ማመን የግድ ይለዋል።

## አምስተኛው ማዕዘን

### በመጨረሻው ቀን ማመን

ይህ ዕለት ከባድነቱንና ፍፁም አስጨናቂነቱን የሚያመላክቱ ብዙ ስያሜዎች አሉት።

በእለተ ትንሳኤ ሰዎች ከመቃብራቸው ወጥተው ከአላህ ፊት ስለሚቆሙ፣ ይህ ዕለት «የቂያማ ዕለት» ተብሎ ይጠራል። «የመጨረሻው ቀን» ተብሎም ይጠራል። አሁን ካለንበት (ከቅርቢቱ) አለም በኋላ ስለሚመጣም፣ በእለቱ ሰዎች ከመቃብራቸው ስለሚነሱ «የትንሳኤ ቀን» «የውመል በዕስ» ተብሏል።

የሰው ልጅ በህይወት ዘመንና ከሞት በኋላ የሚኖርባቸው አገሮች በሶስት ዋና ዋና ክፍሎች ይከፈላሉ፤

- **የዱንያ ሀገር** (ስራ የምንሰራበትና የምንኖርበት ምድራዊ ሀገር)
- **ዳሩል በርዘኽ** (ከሞት እስከ ትንሳኤ ያለው ሀገር)
- **ዳሩል ቀራር** (የመዘውተሪያ ሀገር [ጀነት ወይም እሳት])

«በመጨረሻው ቀን ማመን» ማለት፣ ቀኑ እንደሚከሰት ማመን ብቻ ሳይሆን ከወንጀል ተፀፅቶ በመመለስ ለዚያ ቀን የሚሆን መልካም ስራ በመስራት መዘጋጀት ማለት ነው። ሙስሊሞችን ከዚህ እጅግ በጣም ከባድ ከሆነ ቀን ቅጣትና ውርደት የሚያድናቸው መልካም ስራን መስራትና ከመጥፎ ስራዎች መራቅ እንዲሁም ከሰሩዋቸው ወንጀሎች ተፀፅተው ወደ አላህ መመለስ ብቻ ነው። ነቢዩ ኢብራሒምﷺ እንዲህ ይላሉ፡-

﴿وَلَا تُخْزِنِي يَوْمَ يُبْعَثُونَ ﴿٨٧﴾ يَوْمَ لَا يَنفَعُ مَالٌ وَلَا بَنُونَ ﴿٨٨﴾ إِلَّا مَنْ أَتَى اللَّهَ بِقَلْبٍ سَلِيمٍ ﴿٨٩﴾﴾ الشعراء:٨٧ - ٨٩

***«ሰዎች በሚቀሰቀሱበት ቀን፤ ወደ አላህ በንፁህ ልብ የመጣ ሰው ቢሆን እንጂ ገንዘብም ልጆችም በማይጠቅሙበት ቀንም፣ አታዋርደኝ»*** *(ሹዓራዕ፣ 87-89)*

**ቀኑ ታላቅና ከባድ ቀን ነው::**

﴿يَوْمَ يَفِرُّ ٱلْمَرْءُ مِنْ أَخِيهِ ﴿٣٤﴾ وَأُمِّهِۦ وَأَبِيهِ ﴿٣٥﴾ وَصَٰحِبَتِهِۦ وَبَنِيهِ ﴿٣٦﴾﴾ عبس: ٣٤ - ٣٦

***«ሰው ከወንድሙ፤ ከእናቱም፣ ከአባቱም፣ ከሚስቱም፣ ከልጁም በሚሸሽበት ቀን»*** *(አበሰ፣ 34-36)*

«የመጨረሻ ቀን ወይም ሞቶ መቀስቀስ የሚባል ነገር የለም» የሚል ሰው ከከሀዲዎች ይቆጠራል:: አላህ እንዲህ ይላል:-

﴿زَعَمَ ٱلَّذِينَ كَفَرُوٓاْ أَن لَّن يُبْعَثُواْۚ قُلْ بَلَىٰ وَرَبِّى لَتُبْعَثُنَّ ثُمَّ لَتُنَبَّؤُنَّ بِمَا عَمِلْتُمْۚ وَذَٰلِكَ عَلَى ٱللَّهِ يَسِيرٌ ﴿٧﴾﴾ التغابن: ٧

***«እነዚያ የካዱት በፍፁም የማይቀሰቀሱ መሆናቸውን አሰቡ፤ አይደለም:: 'በጌታዬ እምላለሁ፤ በእርግጥ ትቀሰቀሳላችሁ፤ ከዚያም በሰራችሁትም ሁሉ ትነገራላችሁ፤ ይህም በአላህ ላይ ቀላል ነው' በላቸው::»*** *(ተጋቡን፣ 7)*

ሞቶ መቀስቀስን ለሚክዱ ሰዎች አላህ በቁርዓኑ ምላሽ ሰጥቷቸዋል፤

﴿لَخَلْقُ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلْأَرْضِ أَكْبَرُ مِنْ خَلْقِ ٱلنَّاسِ وَلَٰكِنَّ أَكْثَرَ ٱلنَّاسِ لَا يَعْلَمُونَ ﴿٥٧﴾﴾ غافر: ٥٧

***«ሰማያትንና ምድርን መፍጠር ሰዎችን ከመፍጠር ይልቅ ታላቅ ነው፤ ግን አብዛኞዎቹ ሰዎች አያውቁም::»*** *(ጋፊር፣ 57)*

አላህ ሰዎችን ከሞቱ በኋላ የመቀስቀሱ ጉዳይ የማያጠራጥር መሆኑን ለማስረዳት፣ የሰው ልጅ የራሱን አፈጣጠር በውል እንዲመረምር ጋብዞታል፣ እንዲህ በማለት:-

﴿يَٰٓأَيُّهَا ٱلنَّاسُ إِن كُنتُمْ فِى رَيْبٍ مِّنَ ٱلْبَعْثِ فَإِنَّا خَلَقْنَٰكُم مِّن تُرَابٍ ثُمَّ مِن نُّطْفَةٍ ثُمَّ مِنْ عَلَقَةٍ ثُمَّ مِن مُّضْغَةٍ مُّخَلَّقَةٍ... ﴾ الحج: ٥

***«እናንተ ሰዎች ሆይ! ስለመቀስቀስ በመጠራጠር ውስጥ እንደ ሆናችሁ (አፈጣጠራችሁን ተመልከቱ)፤ እኛ ከአፈር ፈጠርናችሁ፤ ከዚያም ከፍትወት ጠብታ፣ ከዚያም ከረጋ ደም፣ ከዚያም ከቁራጭ ስጋ... ፈጠርናችሁ::»*** *(ሀጅ፣ 5)*

ሞቶ መቀስቀስ፣ ከዚያም በሰሩት መሰረት ዋጋ መሰጠት ባይኖር ኖሮ የሰው ልጅ ሊረዳውና ሊገልፀው ከሚችለው በላይ እጅግ በረቀቀ ጥበብ የተሞላው የዚህ ፍጥረተ አለም መገኘት ወይም መፈጠር ቀልድ በሆነ ነበር:: አንዳንዱ ሰው መልካም ሰርቶ፣ ለልፋቱ ቅንጣት ዋጋ ሳያገኝ፤ ሌላው ወንጀል ሰርቶ በጥፋቱ ምንም ሳይቀጣ ሁሉም አፈር ሆኖ ሊቀር? የግለሰቦችን ሀብትና ንብረት ከማውደምም አልፈው፣ ክብር የተሰጠውን የሰውን ልጅ ህይወት አላግባብ የቀጠፉና ደሙን እንደ ጎርፍ ያፈሰሱ ሁሉ ተገቢ ዋጋቸውን ሳያገኙ አፈር ለብሰውና በስብሰው ሊቀሩ? ይህ ከአላህ ፍትሀዊነትና ጥበበኛነት ጋር ፍፁም የሚሄድ አይደለም:: አላህ እንዲህ ይላል:-

﴿ أَفَحَسِبْتُمْ أَنَّمَا خَلَقْنَٰكُمْ عَبَثًا وَأَنَّكُمْ إِلَيْنَا لَا تُرْجَعُونَ ١١٥ ﴾ المؤمنون: ١١٥

«***የፈጠርናችሁ ለከንቱ መሆኑን፣ እናንተም ወደ እኛ የማትመለሱ መሆናችሁን አሰባችሁን?***» *(ሙዕሚኑን፣ 115)*

አላህ ከሀዲዎችንና ሙሽሪኮችን በመጨረሻ ወደ እርሱ እንደሚመለሱና ሂሳብ እንደሚደረጉ አስጠንቅቋቸዋል:: ይህ ሁሉ የሚያመላክተው ሞቶ መቀስቀስ አይቀሬ መሆኑን ነው:: ይህች ያለንባት አለም የስራ አገር ስትሆን፣ የመጨረሻዋ አለም ደግሞ ዋጋ የሚሰጥባት አገር ናት:: ይህ የአላህ ጥበብ ነው::

የትንሳኤ ቀን ከሞት በኋላ ያለውን ሁሉ ያካትታል:: የትንሳኤ የመጀመሪያው ምዕራፍ የሚጀምረው የሟች ነፍስ ከአካሉ እንደ ተለየች ነው::

**عن أَنَسِ بْنِ مَالِكٍ رضي الله عنه، أَنَّ رَسُولَ اللهِ ﷺ، قَالَ: (إِنَّ الْعَبْدَ إِذَا وُضِعَ فِي قَبْرِهِ، وَتَوَلَّى عَنْهُ أَصْحَابُهُ، وَإِنَّهُ لَيَسْمَعُ قَرْعَ نِعَالِهِمْ، أَتَاهُ مَلَكَانِ، فَيُقعِدَانِهِ فيَقُولاَنِ: مَا كُنْتَ تَقُولُ فِي هذَا الرَّجُلِ (لِمُحَمَّدٍ ﷺ) فَأَمَّا الْمُؤْمِنُ فَيَقُولُ: أَشْهَدُ أَنَّهُ عَبْدُ اللهِ وَرَسُولُهُ فَيُقَالُ لَهُ: انْظُرْ إِلَى مَقْعَدِكَ مِنَ النَّارِ، قَدْ أَبْدَلَكَ اللهُ بِهِ مَقْعَدًا مِنَ الْجَنَّةِ فَيَرَاهُمَا جَمِيعًا) أخرجه البخاري**

ከአነስ ኢብኑ ማሊክ በእንደተዘገበው የአላህ መልዕክተኛ ﷺ እንዲህ ብለዋል «አንድ ሰው ሞቶ ከተቀበረ በኋላ ቀባሪዎች አፈር መልሰው ዘወር እንዳሉ የቀባሪዎችን የጫማ ኮቴ ያዳምጣል፤ ሁለት መላኢካዎች ይመጡና ሟቹን በማስቀመጥ፣ **"ስለዚህ ሰው ስለሙሀመድ ﷺ ምን ስትል ነበር?"** ይሉታል።አማኝ የሆነ ሰው **"የአላህ ባርያና መልዕክተኛ እንደሆኑ እመሰክራለሁ"** ይላቸዋል። እነርሱም **"ልትገባበት የነበረዉን የእሳት መኖርያ ተመልከት፣ አላህ በጀነት መኖርያ ቀይሮልሀል"** ይሉታል። ሰውየውም ሁለቱንም ይመለከታል።» ቡኻሪ ዘግበዉታል

«ጌታህ ማን ነው? ሀይማኖትህ ምንድን ነው? ነብይህ ማን ነው?» የሚሉ ሶስት ጥያቄዎችን እንደሚጠየቅ ተዘግቧል።

እዚህ ላይ አንድ ጥያቄ ሊነሳ ይችላል - «መላኢካዎች፣ እኛ ሳናያቸው እንዴት ወደ መቃብሩ ሊመጡ ይችላሉ?» የሚል። ይህን ጥያቄ በጥያቄ መመለስ ይቻላል፤ «ሞቶ ወደ ተቀበረ ሰው ዘንድ የሚመጡ መላኢካዎችን ይቅርና በአካልህ ውስጥ አብራህ ያለችውን፣ ለህልውናህ መሰረት የሆነችውንና ስትለይህ በድን የምታደርግህን ነፍስህን አይታሀት ታውቃለህን?» አዎ! ማንም ቢሆን ነፍሱን አይቷት አያውቅም። ስለሆነም አለማየታችን የአንድን ነገር አለመኖር ማረጋገጫ ሊሆን አይችልም። ከነፍሳችን ጀምሮ፣ ከእኛ የተሰወሩ ብዙ ነገሮች አሉ። ሌላው ይቅርና ለሰው ልጅ በህልውና ለመኖር ከሚያስፈልጉት ነገሮች ሁሉ፣ ቀዳሚውን ቦታ የሚይዘው አየር ነው። አየር ያጣ ሰው፣ በትንሽ ደቂቃ ውስጥ ህይወቱ ያልፋል። አየር ለሰው ልጅ ይህን ያህል ቅርብና ከምንም በላይ የሚያስፈልገው ነገር ሆኖ ሳለ አየርን ግን ጥቁር ይሁን፣ ቀይ አይቶት አያውቅም። የሰው ልጅ አናቱን የተሸከመለትን አንገቱን ይቅርና ለሁለቱ አይኖቹ እጅግ በጣም ቅርብ የሆነውን የሰውነቱን አካል (አፍንጫውን) አሟልቶ ማየት አይችልም። የሰው ልጅ ይህን ያህል ደካማ ፍጡር ነው። ስለዚህ የማናያቸውን መላኢካዎች በመላክ ሟቹን እንዲጠይቁ ማድረግ፣

ፍጹም የሆነ ጥበብና ችሎታ ባለቤት ለሆነው ለአላህ እጅግ በጣም ቀላል ነው:: *ሙዕሚኖች ከሆን ልባችንን ለአላህ ህግ ክፍት በማድረግ አምነን መቀበል ብቻ ነው::*

*ከመለሰ ሟቹ ሙዕሚን ከሆነ ፈተናውን ያልፋል፤ የተመቻቸ ኑሮም ይኖራል:: ለቀረቡለት ጥያቄዎች ያለምንም ጥርጥር ተስማሚ መልስ ይሰጣል::* ***«ጌታዬ አላህ ነው:: እምነቴ እስልምና ነው:: ነብዩ ሙሀመድﷺ የአላህ መልዕክተኛ ናቸው»*** ይላል:: ከዚያም ተጣሪ ይጣራል፤ **‹‹ባሪያዬ እውነት ተናገረ:: ከጀነት ምንጣፍ አንጥፉለት፤ መቃብሩን የአይን እርቀት ያህል አስፉለት፤ ወደ ጀነት በርን ክፈቱለት››** ይባላል:: የጀነት ሽታዋ ይመጣለታል፤ በጣፋጭ ሽታዋም ይታወዳል:: የጀነት ደረጃውንም ይመለከታል:: ሟቹም **‹‹ጌታዬ ሆይ! ወደ ቤተሰቦቼ (የጀነት ባልደረቦቼ) እና ወደ ሀብቴ (ወደ ሰራሁት መልካም ስራ) እመለስ ዘንድ ቂያማን አቁመው››** ይላል:: ቀብሩም ከጀነት ጨፌዎች፣ አንዱ ጨፌ ይሆንለታል:: የሰው ልጅ የቀብርን ኬላ ካለፈ፣ ከዚያ በኋላ ያለው በጣም ቀላል ነው የሚሆነው::

በዚህ ተቃራኒ ደግሞ ሟቹ ሙናፊቅ ከሆነና በጥርጣሬ ህይወት ሲኖር ከነበረ፣ ሁለቱ መላኢካዎች ከፍ ሲል የተገለፁትን ሶስት ጥያቄዎች ሲያቀርቡለት ምላሹ፣ **«አላውቅም፤ ሰዎች ሲናገሩ ሰምቼ ተናግሪያለሁ እንጂ፣ ምንም የማውቀው ነገር የለኝም››** ይላል:: ይህን የሚልበት ምክንያትም ይህ ሰው በዚህች ምድራዊ ህይወት ሲኖር በልቡ እምነት ስላልነበረው ነው:: **«የሆነ ነገር ሲናገሩ ሰምቼ ተናግሬያለሁ»** የሚል ምላሽ መስጠቱ፣ ሙስሊሞችን መስሎ ሙሰሊሞች የሚናገሩትን ቋንቋ ሲናገርና የሚተገብሩትን ሲፈጽም የነበረ ሙናፊቅ ሰው መሆኑን ያመለክታል:: ሟቹ ትክክለኛ እምነት እስከሌለው ድረስ፣ ቋንቋ አጣርቶ የሚችል ቢሆንም ቀብር ውስጥ ግን ትክክለኛውን መልስ መስጠት የማይችል መሆኑን ያረጋግጣል:: ጥያቄው የቋንቋ ችሎታ መኖር አለመኖር ወይም ቋንቋን አቀላጥፎ የመናገር ወይም ያለመናገር ጉዳይ አይደለም፤ በእምነት ላይ ጸንቶ

የመኖርና ያለመኖር ጉዳይ እንጂ:: ሙናፊቁ ቀብሩ ውስጥ ተገቢውን መልስ መስጠት ሳይችል ሲቀር፣ ልክ እንደ ሙዕሚኑ ተጣሪ ይጣራል፤ **«ባሪያዬ ዋሸ:: ከእሳት የሆነ ምንጣፍ አንጥፉለት፤ ወደ እሳት በርን ክፈቱለት::»** የጀሀነም መጥፎ ሽታዋና መርዟ ይላክለታል:: የቀኙና የግራ ጎን አጥንቶቹ እርስ በርሳቸው እስኪተላለፉ ድረስ ቀብሩ ይጠብበትና ከእሳት ጉድጓዶች አንዱ ጉድጓድ ይሆንበታል::ሚቹም **«የቂያማን (የትንሳኤን) ሰዓት አታቁመው»** ይላል፤ ምክንያቱም ከትንሳኤ በኋላ የሚገጥመውን ከዚህ የከፋ ቅጣት ስለሚያውቀው::

ሙእሚኖችና ሙናፊቆች በቀብር ውስጥ የሚያጋጥማቸውን የተለያየ ሁኔታ በተመለከተ አላህ እንዲህ ይላል:-

﴿ يُثَبِّتُ ٱللَّهُ ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ بِٱلْقَوْلِ ٱلثَّابِتِ فِي ٱلْحَيَوٰةِ ٱلدُّنْيَا وَفِي ٱلْأٓخِرَةِۖ وَيُضِلُّ ٱللَّهُ ٱلظَّٰلِمِينَۚ وَيَفْعَلُ ٱللَّهُ مَا يَشَآءُ ﴿٢٧﴾ ﴾ إبراهيم: ٢٧

***«አላህ እነዚያን ያመኑትን፣ በቅርቢቱም ህይወት በመጨረሻይቱም በተረጋገጠ ቃል ላይ ያጸናቸዋል፤ ከሀዲዎችንም አላህ ያስታቸዋል፤ አላህም የሚሻውን ይሰራል::»*** *(ኢብራሂም፣ 27)*

በዚህ በኩል ከሙእተዚላዎችና የፍልስፍና ሰዎች በስተቀር በቀብር ውስጥ ያለውን ቅጣት የሚያስተባብል የለም:: አህሉሱና በቀብር ውስጥ ጥያቄ ዙሪያ በርካታ ትክክለኛ ሀዲሶችን በማስረጃነት ያቀርባሉ::

ከቀብር ውስጥ ፈተና በተጨማሪ፣ አካላችን በተሟላ ሁኔታ ከመቃብር ወጥቶ ከአላህ ፊት ቀርበን የምንጠየቅ መሆኑን ማመን በመጨረሻው ቀን ከማመን ውስጥ ይካተታል:: ኢስራፊል ለሁለተኛ ጊዜ ሲነፋ ነፍስ እየተስፈነጠረች ወደ አካላችን የምትገባ መሆኑን ማመን የግድ ነው:: አላህ እንዲህ ይላል:-

﴿وَنُفِخَ فِي ٱلصُّورِ فَصَعِقَ مَن فِي ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَمَن فِي ٱلۡأَرۡضِ إِلَّا مَن شَآءَ ٱللَّهُۖ ثُمَّ نُفِخَ فِيهِ أُخۡرَىٰ فَإِذَا هُمۡ قِيَامٞ يَنظُرُونَ ٦٨﴾ الزمر: ٦٨

***«በቀንዱም ይነፋል፤ አላህ የሻው ሲቀር በሰማያት ውስጥ ያለው ፍጡርና በምድርም ውስጥ ያለው ፍጡር ሁሉ፣ በድንጋጤ ይሞታል። ከዚያም በርሱ ሌላ (መነፋት) ይነፋል። ወዲያውም እነርሱ (የሚሰራባቸውን) የሚጠባበቁ ሆነው ይነሳሉ።»*** *(ዙመር፣ 68)*

ከዚያም ወደ መቆሚያው ቦታ ይሰበሰባሉ፤

﴿يَوۡمَ يَخۡرُجُونَ مِنَ ٱلۡأَجۡدَاثِ سِرَاعٗا كَأَنَّهُمۡ إِلَىٰ نُصُبٖ يُوفِضُونَ ٤٣﴾ المعارج: ٤٣

***«ወደ ጣኦቶች እንደሚሽቀዳደሙ ሆነው ከመቃብሮቻቸው ፈጥነው የሚወጡበትን ቀን (እስከሚገናኙ ድረስ ተዋቸው)።»*** *(መዓሪጅ፣ 43)*

በዚህ የመሰብሰቢያ ቦታ ከመጀመሪያው እስከ መጨረሻው ያለው የሰው ልጅ በሙሉ፣ ከእናቱ ሆድ ሲወለድ እንደ ነበረው ሁሉ እርቃኑን፣ ያለ ጫማና ያልተገረዘ ሆኖ ተቀስቅሶ ከጌታው ፊት ለምርመራ ይቀርባል። ይህ የመቆሚያ ቦታ ለከሀዲያን የአምሳ ሺህ ዓመት ያህል ሲረዝምባቸው፣ ለአማኞች ግን ይህ ጊዜ በአንድ ቀን ውስጥ ባሉ ሁለት ተከታታይ ፈርድ ሶላቶች መካከል ያለውን የጊዜ ርቀት ያህል እንዲያጥርላቸው ይደረጋል፡ እናም በሌሎች ላይ የሚደርሰው አሰቃቂ ችግር አይሰማቸውም። አላህ እንዲህ ይላል፡-

﴿ٱلۡمُلۡكُ يَوۡمَئِذٍ ٱلۡحَقُّ لِلرَّحۡمَٰنِۚ وَكَانَ يَوۡمًا عَلَى ٱلۡكَٰفِرِينَ عَسِيرٗا ٢٦﴾ الفرقان: ٢٦

***«እውነተኛው ንግስና በዚያ ቀን ለአልረህማን ብቻ ነው፤ በከሀዲዎችም ላይ አስቸጋሪ ቀን ነው።»*** *(ፉርቃን፣ 26)*

ሰዎች ከአላህ ፊት በሚቀርቡበት ጊዜ የምርመራ ሂደታቸው የተለያየ ነው። ለምሳሌ ሙዕሚኖችን የምርመራ ሂደታቸው በሶስት አይነት መንገድ ይከናወናል፡-

**1ኛ** - ያለምንም ሂሳብና ቅጣት በቀጥታ ጀነት የሚገቡ አሉ:: እነዚህም ሰዎች በሶሂህ ሀዲስ እንደ ተዘገበው ቁጥራቸው ሰባ ሺህ ይደርሳል::

**2ኛ** - ምርመራው በቀላሉ የሚፈጸምላቸው ሰዎች አሉ:: አላህ በቁርዓን እንደሚናገረው፣

﴿فَأَمَّا مَنْ أُوتِيَ كِتَٰبَهُۥ بِيَمِينِهِۦ ﴿٧﴾ فَسَوْفَ يُحَاسَبُ حِسَابًا يَسِيرًا ﴿٨﴾ وَيَنقَلِبُ إِلَىٰٓ أَهْلِهِۦ مَسْرُورًا ﴿٩﴾﴾
الانشقاق: ٧ - ٩

***«መፅሀፉን በቀኙ የተሰጠ ሰውማ፣ በእርግጥ ቀላልን ምርመራ ይመረመራል፤ ወደ ቤተሰቦቹም ተደሳች ሆኖ ይመለሳል::»*** *(ኢንሽቃቅ፣ 7-9)*

**3ኛ** - ስራቸው እያንዳንዱ በጥብቅ የሚመረመርባቸው ሰዎች አሉ:: ነብያችን ﷺ በቡኻሪ ዘገባ እንደ ተናገሩት **«እያንዳንዷን ስራውን ሂሳብ የተደረገ ይቀጣል::»**

የሙዕሚኖች ሂሳብ **«ሂሳቡ ሙዋዘናህ»** ይባላል:: **«ሂሳቡ ሙዋዘናህ»** የሚመዘን መልካም ስራ ያለ መሆኑን ያመለክታል:: የከሀዲ ካፊሮች ሂሳብ **«ሂሳብ አተቅሪር»** ይባላል:: **«ሂሳብ አተቅሪር»** የሚመዘን መልካም ስራ አለመኖሩን ያመለክታል:: ስለሆነም የከሀዲዎች ስራ ለሚዛን አይቀርብም:: ከአላህ ፊት የሚቀርቡት የሰሩትን ወንጀል እንዲያዩና በራሳቸው ላይ እንዲመሰክሩ ለማድረግ ብቻ ነው::

በመጨረሻው ቀን ማመን፣ ከጀሀነም በላይ የተዘረጋ **«ሲራጥ»** የሚባል ድልድይ ያለ መሆኑን ማመንን ይጨምራል:: ሁሉም የሰው ልጅ በሲራጥ ላይ ያልፋል:: በዚህ ከሰይፍ በሰላ፣ ከፀጉር በቀጠነ ድልድይ ላይ እንደ ስራቸው መጠን በፍጥነት ወይም እየተንኳተቱ የሚያልፉ ሲኖሩ፣ ማለፍ ተስኗቸው ወደ ጀሀነም የሚወርዱም አሉ:: በሶሂህ ሀዲስ እንደ ተዘገበው ከሰዎች መካከል፣

- እንደ መብረቅ ብልጭታ የሚያልፉ አሉ::
- ልክ እንደ ንፋስ ፍጥነት የሚያልፉ አሉ::
- ልክ እንደ ፈጣን ፈረስ ጋላቢ የሚያልፉ አሉ::

- ልክ እንደ ግመል ጋላቢ የሚያልፉ አሉ፡፡
- ልክ እንደ ሯጭ የሚያልፉ አሉ፡፡
- በእግር አካሄድ (በመራመድ) የሚያልፉ አሉ፡፡
- እየተንፏቀቁ የሚሄዱ አሉ፡፡
- በመንጠቆ እየተያዙ ወደ ጀሀነም እሳት የሚወረወሩ አሉ፡፡

## ስድስተኛው ማዕዘን

### *በቀደር (በአላህ ውሳኔ) ማመን*

«**ቀደር**» ማለት «አላህ እስከ ትንሳኤ ቀን ድረስ የሚሆነውን ወይም የሚከሰተውን ነገር በሙሉ ወስኖታል» ማለት ነው፡፡ ፍጥረተ አለሙ ከመፈጠሩ በፊት እስከ ትንሳኤ ቀን ድረስ የሚሆነውና የሚከሰተው ሁሉ በለውሀል መህፉዝ (በተጠበቀው ሰሌዳ) ላይ ተመዝግቦ ይገኛል፡፡ አላህﷻ እንዲህ ይላል፡-

﴿إِنَّا كُلَّ شَيْءٍ خَلَقْنَٰهُ بِقَدَرٍ ﴿٤٩﴾﴾ القمر: ٤٩

«*እኛ ሁሉን ነገር በልክ ፈጠርነው፡፡*» (*ቀመር፣ 49*)

ነገሮች ሁሉ እንዲሁ በአጋጣሚና በዘፈቀደ የሚፈጸሙ አይደሉም፣ በአላህ እቅድና ውሳኔ እንጂ፡፡ አላህﷻ በቁርዓኑ እንዲህ ይላል፡-

﴿مَآ أَصَابَ مِن مُّصِيبَةٍ فِى ٱلْأَرْضِ وَلَا فِىٓ أَنفُسِكُمْ إِلَّا فِى كِتَٰبٍ مِّن قَبْلِ أَن نَّبْرَأَهَآ ۚ إِنَّ ذَٰلِكَ عَلَى ٱللَّهِ يَسِيرٌ ﴿٢٢﴾﴾ الحديد: ٢٢

«***በምድርም፣ በነፍሶቻችሁም መከራ (ማንንም) አትነካም፤ ሳንፈጥራት በፊት በመፅሀፍ የተመዘገበች ብትሆን እንጂ፡፡ ይህ በአላህ ላይ ገር ነው፡፡***» (ሀዲድ፣ 22)

በቀደር ማመን አራት ነገሮችን ያካትታል፡-

**1ኛ** - በአላህ ፍፁማዊ እውቀት ማመን፤

- አላህ በእውቀቱ ሁሉንም ነገር አካቧል፡፡

**2ኛ** - በለውሀል መህፉዝ (በተጠበቀው ሰሌዳ) ማመን፤

- እስከ ትንሳኤ ድረስ የሚከናወነውን ነገር ሁሉ አላህ በለውሀል መህፉዝ መዝግቦታል፡፡

**3ኛ** - በአላህ ፍቃድ(መሽአ) እና ኢራዳ ማመን፤
○እርሱ የሻው ይሆናል፤ እርሱ ያልሻው አይሆንም::
**4ኛ** - አላህ ነገሮችን ሁሉ የፈጠረ መሆኑን ማመን፤
○ከእርሱ ጋር ሌላ ፈጣሪ የለም::
አላህﷻ እንዲህ ይላል፡-

﴿ٱللَّهُ خَٰلِقُ كُلِّ شَيۡءٖۖ وَهُوَ عَلَىٰ كُلِّ شَيۡءٖ وَكِيلٞ ٦٢﴾ الزمر: ٦٢

«***አላህ የነገሩ ሁሉ ፈጣሪ ነው::እርሱም በነገሩ ሁሉ ላይ አስተናባሪ ነው***»*(ዙመር፣62)*

በአላህ ውሳኔ ያመነ ሰው ፍፁም የሆነ የህሊና እረፍት ያገኛል:: በፀፀት እሳት፣ በቁጭት ረመጥ አይቃጠልም:: ባለፈው ነገር እንደማያዝን ሁሉ፣ ባገኘው ነገር ከልክ በላይ አይደሰትም:: በተቃራኒው በቀዷና በቀደር ያላመነ ሰው ባጣው ነገር ይበሳጫል፤ ንዴትና ብስጭቱን ገሀድ የሚያወጡ አስቀያሚ ነገሮችን ይናገራል ወይም ይፈጽማል:: ሆኖም አንድ ግለሰብ በብስጭት ጦፎ፣ ፊቱን ቢቧጭር፣ ልብሱን ቢቀድና እየዬውን ቢያቀልጥ ያለፈውን ነገር መመለስ አይችልም፤ ትርፉ ንዴትና ኪሳራ ብቻ ነው:: ከአላህ ዘንድ ምንዳን አጥቶ ለውርደትና ለኪሳራ የተጋለጠ ይሆናል:: በቀዷና በቀደር የማያምን ሰው ስቃይ ባለፈው ነገር መቆጨትና መበሳጨት ብቻ አያበቃም:: ወደ ፊት ስለሚመጣው ነገር ልቡ በፍርሀትና በስጋት እየተናወጠ ይፈተናል:: ማንኛውንም ነገር ስለሚፈራ ጅሀድ ወጥቶ መታገል አይችልም::

عن أبي العباس عبدالله بن عباس رضي الله عنهما قال كنت خلف النبي صلى الله عليه وسلم يوما فقال لي يا غلام إني أعلمك كلمات احفظ الله يحفظك احفظ الله تجده تجاهك إذا سألت فاسأل الله وإذا استعنت فاستعن بالله واعلم أن الأمة لو اجتمعت على أن ينفعوك بشيء لم ينفعوك إلا بشيء قد كتبه الله لك إن اجتمعوا على أن يضروك بشيء

لم يضروك إلا بشيء قد كتبه الله عليك رفعت الأقلام وجفت الصحف رواه الترمذي وقال حديث حسن صحيح

አብዱላህ ብን አባስ ባስተላለፉት ሀዲስ እንዲህ ብለዋል፤ አንድ ቀን ከነብያችንﷺ ኋላ ነበርኩኝ ‘አንተ ልጅ ሆይ!’ እኔ ተከታዮቹን ቃላት አስተምርሀለሁ አድምጥ አሉ፤‹‹**ከጠየቅክ አላህን ብቻ ጠይቅ፤ መታገዝ ከፈለግህ በአላህ ብቻ ታገዝ፤ ሰዎች ሁሉ ተሰባስበው ‘እንጥቀምህ’ ቢሉ፣ አላህ ለአንተ የጻፈልህን ካልሆነ በስተቀር ምንም ሊጠቅሙህ እንደማይችሉ እወቅ። ሰዎች ሁሉ ተሰባስበው አንተን ‘እንጉዳ’ ቢሉ፣ አላህ እንድትጎዳ የጻፈው ነገር እስከሌለ ድረስ ሊጎዱህ አይችሉም። ብዕሩ ተነስቷል፤ ቀለሙም ደርቋል።››** ቲርሚዚይ ዘግበውታል

በቀዷና በቀደር ማመን ጥንካሬን ያላብሳል፤ የህሊና ሰላምን ያጎናፅፋል። እምነትና ተወኩል (በአላህ መመካት) እንዲኖር ያደርጋል። በቀደር የሚያምን ሙስሊም ባጋጠመው መጥፎ ነገር፣ የቁጭት እርምጃ ሊወስድ ይቅርና አይበሳጭም። ለዚህም ነው ነብያችንﷺ ሙስሊም ከአቡሁረይራ በዘገቡት ሀዲስ እንዲህ ብለዋል፤

عَنْ أَبِي هُرَيْرَةَ قَالَ: قَالَ رَسُولُ اللهِ ﷺ: " الْمُؤْمِنُ الْقَوِيُّ خَيْرٌ وَأَحَبُّ إِلَى اللهِ مِنَ الْمُؤْمِنِ الضَّعِيفِ وَفِي كُلٍّ خَيْرٌ، احْرِصْ عَلَى مَا يَنْفَعُكَ وَاسْتَعِنْ بِاللهِ وَلَا تَعْجَزْ، وَإِنْ أَصَابَكَ شَرٌّ فَلَا تَقُلْ لَوْ أَنِّي فَعَلْتُ كَذَا وَكَذَا قُلْ قَدَّرَ اللهُ وَمَا شَاءَ اللهُ فَعَلَ، فَإِنَّ لَوْ تَفْتَحُ عَمَلَ الشَّيْطَانِ " رَوَاهُ مُسْلِمٌ

**«በሚጠቅምህ ነገር ላይ ጉጉት ይኑርህ፤ በአላህ ታገዝ፤ ደካማና ስልቹ አትሁን፤ አንድ ነገር ባጋጠመህ ጊዜ ‘ይህን ነገር እንዲህ ባደርገው ኖሮ…’ አትበል። ነገር ግን ‘አላህ የወሰነው ሆነ፤ አላህ የፈለገውን ይሰራል’ በል። ‘እንዲህ ቢሆን ኖሮ’ የሚለው ንግግር ለሰይጣን ስራ በር ይከፍታል»** ሙስሊም ዘግበዉታል

አንተ የአሰብከው ጉዳይ እንዲሳካልህ ምክንያት የሆኑ ነገሮችን ከተገበርክ በኋላ፣ ባልከው መንገድ ሳይፈጸም ቢቀር፣ አላህ ያልሻው (ያልፈቀደው) ነገር ሊፈጸም እንደማይችል መገንዘብ አለብህ። እንዲፈጸምልህ የፈለከውን ጉዳይ በተመለከተ፣ ለአንተ መልካሙ ነገር ጉዳዩ አለመፈጸሙ ሊሆን ይችላል።

አንድ ሙእሚን ህይወቱን መምራት ያለበት ማንኛውንም ጉዳይ ወደ አላህ በማስጠጋትና በአላህ ብቻ በመመካት መሆን አለበት። ይህ ማለት ግን ከእሱ የሚጠበቅበትን ተግባር መስራት የለበትም ማለት አይደለም። አንድ ነገር ያለምክንያት እንደማይገኝ ማመን አለበት። ለአለመው ነገር መሳካት ምክንያት (ሰበብ) የሆኑ ነገሮችን ለግብር ይውጣ ያህል መስራት ተገቢ አይደለም። በቁርጠኝነት መስራት አለበት። ሆኖም ግን ምክንያት በሆኑ ነገሮች ላይ ብቻ መደገፍና ሙሉ በሙሉ እምነት መጣል ተገቢ አይደለም። ከእሱ የሚጠበቀው ለአለመው ጉዳይ መሳካት ምክንያት ሊሆኑ የሚችሉ ነገሮችን እያስገኘ በአላህም መመካት ነው።

በአላህ ቀዷና ቀደር እምነት ውስጥ ሌላው የሚካተተው ጉዳይ፣ ባሮች ስራቸውን በፍላጎታቸው መርጠው የሚተገብሩ መሆናቸው ነው። «ጀብርያ» የሚባሉ ቡድኖች «የሰው ልጆች ተግባራቸውን የሚፈጽሙት አላህ አስገድዷቸው ነው» ይላሉ። ይህ በጣም የተሳሳተ አመለካከት ነው። የሰው ልጅ አለማዊ ህይወቱን የሚመራው አስቦና አቅዶ በራሱ ፍላጎት እንደ ሆነ ሁሉ፣ አምልኮታዊ ተግባሩን ማለትም ሶላቱን የሚሰግደው፣ ጾሙን የሚያመው፣ ዘካውን የሚሰጠውና ሌሎች ኢስላማዊ ተግባራትን የሚፈፅመው በራሱ ፍላጎት መሆኑ ለማንም ግልጽ ነው። ከዚህ በተቃራኒ አንድ ሙስሊም ባይሰግድ፣ ባይፆም ወይም የወንጀል ተግባር (ስርቆት፣ ዚና፣ ወዘተ…) ቢፈፅም በራሱ ፍላጎትና ምርጫ ነው የፈፀመው፤ ማንም ያስገደደው አካል የለም።

የሰው ልጅ ራሱ መርጦ የሰራው ተግባር ውጤቱ መልካም ከሆነ ይመነዳል፤ መጥፎ ከሆነም ይቀጣል፡፡ «ሁሉም የስራውን ያገኛል» የሚባለውም ለዚህ ነው፡፡ ሆኖም ወንጀል የሰራው ሰው በሀይል የተገደደ፣ ለአቅመ አዳም ያልደረሰ ህፃን፣ አእምሮው ጤነኛ ያልሆነ ወይም በእንቅልፍ ላይ ያለ ሰው ከሆነ በሰራው ሀጢያት ተጠያቂ አይደለም፡፡

«ሙእተዚላዎች» በበኩላቸው ከጀብርያዎች በተቃራኒ «የአላህ ቀዷና ቀደር የሚባል ነገር የለም፤ የሰው ልጅ ስራውን የሚፈጥረው እራሱ ነው» ይላሉ፡፡

አህሉሱና ያላቸው አቋም መካከለኛ ነው፡፡ የሰው ልጆች እቅድንና ምክንያትን መሰረት አድርገው ስራቸውን ይሰራሉ፡፡ ነገር ግን ስራው ስኬት ሊኖረው የሚችለው የአላህ ፈቃድ ሲኖር ብቻ ነው፡፡

ከዚህ በላይ የተዘረዘሩት የኢማንና የኢስላም ማዕዘናት ናቸው፡፡ ኢማንና ኢስላም በዲኑ ውስጥ ታላላቅ ደረጃዎች ናቸው፡፡ ሁለቱም በአንድ ላይ ከተወሱ፣ ኢስላም በገሀድ የሚሰራ ተግባር፣ ኢማን ደግሞ የልብ ተግባር ተብሎ ሊተረጎም ይችላል፡፡ አንዱ ከሌላው ተነጥሎ ከተወሳ ግን፣ አንዱ ካለ ሌላው ትርጉም ስለሌለው የሌላውን ትርጉም ያቅፋል፡፡ ልክ በሀዲሱ ጅብሪል ላይ እንደ ተገለጸው ማለት ነው፡፡

እዚህ ላይ «ከሽርክ በታች የሆነ ወንጀል ወይም ከባድ ሀጢያት የሚሰሩ ሰዎች ‘ሙስሊም ወይንስ ሙዕሚን ነው’ የሚባሉት» የሚል ጥያቄ ሊነሳ ይችላል፡፡ በዚህ ጉዳይ ላይ አህሉሱና የሚያራምዱት አቋም ትክክለኛው ጎዳና ነው፡፡ በአህሉ ሱና አቋም መሰረት ከሽርክ በታች የሆነ ወንጀል የፈፀመ ሰው ሙስሊም ነው፡፡ ከኢማን አንፃር ደግሞ «እምነቱ የጎደለ ሙዕሚን» ይባላል፤ «ለምን?» ቢሉ እምነት ይጨምራል፣ ይቀንሳልና፡፡ አላህﷻ በቁርዓኑ እንዲህ ይለናል፡-

﴿إِنَّمَا ٱلۡمُؤۡمِنُونَ ٱلَّذِينَ إِذَا ذُكِرَ ٱللَّهُ وَجِلَتۡ قُلُوبُهُمۡ وَإِذَا تُلِيَتۡ عَلَيۡهِمۡ ءَايَٰتُهُۥ زَادَتۡهُمۡ إِيمَٰنٗا وَعَلَىٰ رَبِّهِمۡ يَتَوَكَّلُونَ ٢﴾ الأنفال: ٢

*«ፍፁም ምዕመናን እነዚያ አላህ በተወሳ ጊዜ ልቦቻቸው የሚፈሩት፣ በነሱም ላይ አንቀፆቻችን በተነበቡ ጊዜ እምነትን የሚጨምሩላቸው፣ በጌታቸውም ላይ ብቻ የሚመኩት ናቸው::» (አንፋል፣ 2)*

﴿وَمَا جَعَلۡنَآ أَصۡحَٰبَ ٱلنَّارِ إِلَّا مَلَٰٓئِكَةٗۙ وَمَا جَعَلۡنَا عِدَّتَهُمۡ إِلَّا فِتۡنَةٗ لِّلَّذِينَ كَفَرُواْ لِيَسۡتَيۡقِنَ ٱلَّذِينَ أُوتُواْ ٱلۡكِتَٰبَ وَيَزۡدَادَ ٱلَّذِينَ ءَامَنُوٓاْ إِيمَٰنٗاۙ وَلَا يَرۡتَابَ ٱلَّذِينَ أُوتُواْ ٱلۡكِتَٰبَ وَٱلۡمُؤۡمِنُونَ﴾ المدثر: ٣١

*‹‹የእሳትን ዘበኞች መላእክት እንጂ ሌላ አላደረግንም፤ ቁጥራቸውንም ለነዚያ ለካዱት መፈተኛ እንጂ አላደረግንም:: ይህም እነዚያ መጽሀፍን የተሰጡት እንዲያረጋግጡ፣እነዚያም ያመኑት እምነትን እንዲጨምሩ፣ እነዚያም መጽሃፍን የተሰጡት እና ምእመናኖቹ እንዳይጠራጠሩ...» (ሙደሲር፣ 31)*

አዎ! እምነት ይጨምራል፣ ይጎድላል፤ የብናኝ ክብደት እስከሚደርስም ይቀንሳል:: በሀዲስም ነብያችንﷺ እንዲህ ይላሉ፤

عن أبي هريرة رضي الله عنه عن النبي ﷺ قال: «الإِيمَانُ بِضْعٌ وَسَبْعُونَ أَوْ بِضْعٌ وَسِتُّونَ شُعْبَةً فَأَفْضَلُهَا قَوْلُ لاَ إِلَهَ إِلاَّ اللَّهُ وَأَدْنَاهَا إِمَاطَةُ الأَذَى عَنِ الطَّرِيقِ وَالْحَيَاءُ شُعْبَةٌ مِنَ الإِيمَانِ» رواه البخاري ومسلم

**«እምነት ስልሳ ማናምን ወይም ሰባ ምናምን ዘርፎች አሉት፤ ከፍተኛውና ትልቁ ላኢላሀ ኢለላህ የሚለው ንግግር ነው፤ ዝቅተኛውና አነስተኛው ደግሞ አስቸጋሪን ነገር (እንቅፋትን) ከመንገድ ማስወገድ ነው:: ትህትና ከእምነት አንዱ ዘርፍ ነው»** ቡኻሪና ሙስሊም ዘግበውታል

ይህ የሚያመለክተው እምነት እንደሚጨምርና እንደሚቀንስ ነው:: ይህ የአህሉ ሱና አቋም ከሙርጅዓዎች አቋም ተቃራኒ ነው:: ሙርጅዓዎች «እምነት አይጨምርም አይቀንስም:: እምነት አንድ ነው፤ ተግባር ከእምነት አይቆጠርም:: እምነት ከቀልብ

ውስጥ ያለ ነገር ብቻ ነው» ይላሉ:: ከመረጃ አንፃር ስናየው፣ ይህ አባባል ያለ ምንም ጥርጥር ስህተት ነው:: ከዚህ በተቃራኒው የኸዋሪጅ ቡድን «ከሽርክ ውጭ ያለም ቢሆን፣ ከባድ ወንጀልን የሰራ ሰው ከሀዲ ነው» ይላሉ:: ኢማን እንዳለው ሙሉ በሙሉ አይቀበሉም:: ሙርጅዓዎች በበኩላቸው «የፈለገውን ወንጀል ቢሰራ ሙሉ እምነት አለው፤ ከኢስላም ጎዳና አይወጣም» ይላሉ:: ይህ በነርሱ መካከል ያለ ተቃርኖ ነው:: ትክክለኛው የሀቅ ባለቤቶች አቋም ግን «ኢማን ይጨምራል፤ ይቀንሳል» የሚል ነው::

«ሙዕተዚላ» የሚባለው ፊርቃ (ቡድን) በበኩሉ በአዲስ መልክ ከሁለቱም ቡድኖች የተለየ ሀሳብ ይዞ ብቅ ብላል:: «ታላላቅ ወንጀሎችን የሚሰሩ ሰዎችን 'ሙዕሚን' አንላቸውም፣ 'ከሀዲም' አንላቸውም:: በሁለቱ መካከል ያለ ነው» ይላሉ:: ሙዕተዚላዎችን ከኸዋሪጆች ጋር የሚያስማማቸው ነጥብ «አንድ ሰው በወንጀል ላይ ሆኖ ወደ አላህ በተውበት ሳይመለስ ከሞተ፣ በእሳት ውስጥ ዘውታሪ ነው» የሚል አቋም መያዛቸው ነው:: «በምድራዊ ህይወት ግን በሙእሚንና በካፊር መካከል ያለ ቦታ ነው ያለው» ይላሉ:: ይህ አመለካከት ጤናማ አእምሮ ያለው ሰው የሚያስበው ነው ለማለት አስቸጋሪ ነው:: አላህﷻ እንዲህ ይላል፡-

﴿هُوَ ٱلَّذِى خَلَقَكُمْ فَمِنكُمْ كَافِرٌ وَمِنكُم مُّؤْمِنٌ ۚ وَٱللَّهُ بِمَا تَعْمَلُونَ بَصِيرٌ ۝٢﴾ التغابن: ٢

***«እርሱ ያ የፈጠራችሁ ነው:: ከናንተም ከሃዲ አለ፤ ከናንተም አማኝ አለ:: አላህም በምትሰሩት ሁሉ ተመልካች ነው::» (ተጋቡን፣ 2)***

## ሶስተኛው የጅብሪል ጥያቄ

### «ስለኢህሳን ይንገሩኝ?»

ጅብሪል፣ ለነብዩﷺ ያቀረበው ሶስተኛው ጥያቄ፣ **«ስለኢህሳን ይንገሩኝ?»** የሚል ነው:: **«ኢህሳን»** ከፍተኛው የኢማን ደረጃ

ነው:: «ኢህሳን» ማለት «አንድን ነገር አጥርቶና አሟልቶና አሳምሮ መስራት» ማለት ነው:: አላህ እንዲህ ይላል:-

﴿ ٱلَّذِيٓ أَحۡسَنَ كُلَّ شَيۡءٍ خَلَقَهُۥۖ وَبَدَأَ خَلۡقَ ٱلۡإِنسَٰنِ مِن طِينٖ ﴿٧﴾ ﴾ السجدة: ٧

*‹‹ያ የፈጠረውን ነገር ሁሉ ያሳመረ፣ የሰውንም ፍጥረት ከጭቃ የጀመረው ነው::›› (አሰጅዳህ፣ 7)*

«ኢህሳን» ሁለት መገለጫዎች አሉት ‘በአላህና በሰዎች’ እና ‘በሰዎች በራሳቸው’ መካከል:: በሰዎችና በአላህ መካከል ያለው «ኢህሳን» የሚገለጸው በአላህ ሳያጋሩ እርሱን በብቸኝነት በማምለክ ነው:: በሰዎች መካከል ያለው ኢህሳን ደግሞ በመደጋገፍና በመረዳዳት፣ በመጠያየቅ፣ በመመካከርና ዲናዊ እውቀትን በመለገስ ሊገለጽ ይችላል:: አላህﷻ እንዲህ ይላል:-

﴿وَأَنفِقُواْ فِي سَبِيلِ ٱللَّهِ وَلَا تُلۡقُواْ بِأَيۡدِيكُمۡ إِلَى ٱلتَّهۡلُكَةِ وَأَحۡسِنُوٓاْۚ إِنَّ ٱللَّهَ يُحِبُّ ٱلۡمُحۡسِنِينَ ﴿١٩٥﴾ ﴾ البقرة: ١٩٥

*«በአላህም መንገድ ለግሱ:: በእጆቻችሁም (ነፍሶቻችሁን) ወደ ጥፋት አትጣሉ:: በጎ ስራንም ስሩ፤ አላህ በጎ ሰሪዎችን ይወዳልና::» (በቀራህ፣ 195)*

በምንሰራው የኢባዳ ስራ ውስጥ ቢድዓ (አዲስ ፈጠራ) ከጨመርንበት፣ በምንም ተአምር ኢህሳን ሊኖር አይችልም::

﴿ بَلَىٰۚ مَنۡ أَسۡلَمَ وَجۡهَهُۥ لِلَّهِ وَهُوَ مُحۡسِنٞ فَلَهُۥٓ أَجۡرُهُۥ عِندَ رَبِّهِۦ وَلَا خَوۡفٌ عَلَيۡهِمۡ وَلَا هُمۡ يَحۡزَنُونَ ﴿١١٢﴾ ﴾ البقرة: ١١٢

*«...እርሱ በጎ ሰሪ(ሙህሲን) ሆኖ ፊቱን ለአላህ የሰጠ ሰው፣ ለርሱ በጌታው ዘንድ ምንዳው አለው::በነርሱም ላይ ፍርሃት የለባቸውም፤እነርሱም አያዝኑም::» (በቀራህ፣112)*

አንድ ስራ መልካም የሚባለው ለአላህ ተብሎ የተሰራና የተሰራበት መንገድም ሱናን መሰረት ያደረገ ሲሆን ነው::

عن عائشة رضي الله قالت قال رسول الله ﷺ (من عمل عملاً ليس عيه أمرنا فهو رد) رواه مسلم

‹‹ትዕዛዛችን የሌለበትን ስራ የሰራ (ስራው) ተመላሽ ነው (ተቀባይነት የለውም)::›› ሙስሊም ከዓኢሻ ዘግበውታል::

በጅብሪል ሀዲስ ውስጥ ነብዩ ﷺ የኢህሳንን ምንነት **«አላህን ልክ እንደምታየው ሆነህ ልታመልክ ነው»** በሚል አጭር፣ ነገር ግን ሰፊ ትንታኔን በያዘ አነጋገር ተርጉመውታል:: በዚህ የረሱልﷺ ትርጓሜ መሰረት «ኢህሳን» በአላህና በባሪያው መካከል መኖር ያለበትን ጤናማ ግንኙነት ያመላክታል:: ስለዚህም «ኢህሳን» የሙሉ ኢማንና የእምነት ጥንካሬ መገለጫ ነው::

አንድ ነገር ፊት ለፊታችን እያለና ከእኛ በአካል ሲርቅ ያለው ስጋታችንና ፍርሀታችን ልዩነት አለው:: አላህንም ስናመልከው ልክ ከፊት ለፊታችን እንደምናየው አድርገን መሆን አለበት:: አለበለዚያ አላህ በዚህች በእንከን በተሞላች፣ በወንጀል በቆሸሸች ምድራዊ ህይወት የሚታይ አምላክ አይደለም፤ የሰው ልጆችም በዚህች የምድራዊ ህይዎት አላህን የማየት አቅሙ የላቸውም:: እዚህ ላይ ነብዩ ሙሳንعليه السلام እንደ አብነት ማንሳት ይቻላል:: ጌታቸውን ጠየቁ፤«ጌታዬ ሆይ! ተገለጽልኝ፤ ወደ አንተ እየተመለከትኩ ነውና» በማለት:: ከአላህ ያገኙት ምላሽ፤ ማየት እንደማይቻላቸው ያሳወቃቸው ነበር::

﴿وَلَمَّا جَاءَ مُوسَى لِمِيقَاتِنَا وَكَلَّمَهُ رَبُّهُ قَالَ رَبِّ أَرِنِي أَنْظُرْ إِلَيْكَ قَالَ لَنْ تَرَانِي وَلَكِنِ انْظُرْ إِلَى الْجَبَلِ فَإِنِ اسْتَقَرَّ مَكَانَهُ فَسَوْفَ تَرَانِي فَلَمَّا تَجَلَّى رَبُّهُ لِلْجَبَلِ جَعَلَهُ دَكًّا وَخَرَّ مُوسَى صَعِقًا فَلَمَّا أَفَاقَ قَالَ سُبْحَانَكَ تُبْتُ إِلَيْكَ وَأَنَا أَوَّلُ الْمُؤْمِنِينَ﴾ الأعراف: 143

***«ሙሳም ለቀጠሮኣችን በመጣና ጌታውም ባነጋገረው ጊዜ፦ «ጌታዬ ሆይ! አሳየኝ ወደ አንተ እመለከታለሁና» አለ:: (አላህም)፦ «በፍጹም አታየኝም ግን ወደ ተራራው ተመልከት:: በስፍራውም ቢረጋ በእርግጥ ታየኛለህ» አለው:: ጌታው ለተራራው በተገለጸ ጊዜ እንኩትኩት አደረገው:: ሙሳም ጮሆ ወደቀ:: በአንሰራራም ጊዜ***

*«ጥራት ይገባህ:: ወዳንተ ተመለስኩ:: እኔም (በወቅቱ) የምእምናን መጀመሪያ ነኝ» አለ::» (በቀራህ፣112)*

ሆኖም ነገ በትንሳኤ ቀን ሙዕሚኖች አላህን በገሀድ ያዩታል:: እንዲያውም በጀነት ካለው ጣፋጭ ምግብና ፀጋ ሁሉ ለሙእሚኖች የሚያስደስታቸው አላህን ማየት ነው:: ከሀዲዎች ግን ጌታቸውን የማየት ምንም እድል የላቸውም:: አላህﷻ በቁርዓኑ እንዲህ ይላል:-

﴿ كَلَّآ إِنَّهُمۡ عَن رَّبِّهِمۡ يَوۡمَئِذٖ لَّمَحۡجُوبُونَ ١٥ ﴾ المطففين: ١٥

***«ይከልከሉ፤ እነርሱ በዚያ ቀን ጌታቸውን ከማየት ተጋራጆች ናቸው::»*** *(ሙጦፊፊን፣ 15)*

ረሱል ﷺ ለጅብሪል የሰጡት መልስ፣ '***አላህን ልክ እንደምታየው ሆነህ ልትገዛው ነው፤ አንተ ባታየው እንኳን እሱ ያይሀልና***' የሚል ነው:: ኢህሳንን በሚመለከት ባጭሩ ለአንድ ሙስሊም በላጩ ነገር፣ አላህን ልክ ከፊት-ለፊቱ እንደሚያየው አድርጎ ማምለክ ነው:: አላህን ልክ የሚያየው ያህል አድርጎ ለመገዛት የእምነት ጥንካሬው ከሌለው፣ ነብዩ ﷺ የኢህሳንን

## ስድስተኛው የጅብሪል ጥያቄ

ሁለተኛ ደረጃ አስቀምጠዋል፤ «**አንተ ባታየውም እንኳ እርሱ ያይሀልና**» (አላህ እንደሚያይህ በማሰብና በመፍራት ተገዛው):: ከዚህ የምንረዳው «አላህ ያየኛል» ብለን ማምለክ እንዳለብን ነው፤ አላህ ሰሚም፣ ተመልካችም ነውና:: በማንኛውም ቦታ ብንሆን «አላህ ተመልካችና ተቆጣጣሪዬ ነው» ብለን ትእዛዙን መፈጸምና የከለከለውን መከልከል አለብን::

### «እስኪ ስለቂያማ (ትንሳኤ) ስአት ይንገሩኝ?»

ጅብሪል፣ ለነብዩ ﷺ ካቀረበላቸው ጥያቄዎች መካከል «**ስለቂያማ ስአት ይንገሩኝ**?» የሚለው ይገኝበታል:: «ሰአቱ» (ቂያማ) ሁሉም ከመቃብሩ ተነስቶ ከጌታው ፊት ለፍርድ የሚቆምበት ቀን፣ የዚህች ምድራዊ ህይወት ዱንያ ፍጻሜና የመጨረሻው አለም

መጀመሪያ ነው:: በዚህ ማመን ደግሞ ከአርካነል ኢማን (ከኢማን ማእዘናት) አንዱ ነው:: በዚህ ያላመነ ሙስሊም አይባልም:: አላህﷻ እንዲህ ይላል፡-

﴿زَعَمَ ٱلَّذِينَ كَفَرُوٓاْ أَن لَّن يُبۡعَثُواْۚ قُلۡ بَلَىٰ وَرَبِّي لَتُبۡعَثُنَّ ثُمَّ لَتُنَبَّؤُنَّ بِمَا عَمِلۡتُمۡۚ وَذَٰلِكَ عَلَى ٱللَّهِ يَسِيرٞ ٧﴾ التغابن: ٧

***«እነዚያ የካዱት በፍጹም የማይቀሰቀሱ መሆናቸውን አሰቡ፤ አይደለም:: 'በጌታዬ እምላለሁ በርግጥ ትቀሰቀሳላችሁ፤ ከዛም የሰራችሁትን ሁሉ ትነገራላችሁ:: ይህም በአላህ ላይ ቀላል ነው' በላቸው::» (ተጋቡን፣ 7)***

የሰው ልጅ በመጨረሻው አለም ማመኑ ብቻ በቂ አይደለም፤ ለመጨረሻው አለም መዘጋጀት አለበት:: መልካም ስራዎችን በመስራት፣ ወደ አላህ በተውበት (በጸጸት) መመለስ አለበት::

የቂያማን ሰዓት ከአላህ በስተቀር ማንም የሚያውቃት የለም:: ምክንያቱም ለሰው ልጆች ቂያማ የሚቆምበትን ሰዓት ማወቃቸው ምንም የሚጠቅማቸው ነገር የለም:: ጠቃሚው ጉዳይ ቂያማ መኖሩን አምኖ ለዚያ ቀን መዘጋጀት ብቻ ነው:: አላህ እንዲህ ይላል፡-

﴿يَسۡـَٔلُونَكَ عَنِ ٱلسَّاعَةِ أَيَّانَ مُرۡسَىٰهَاۖ قُلۡ إِنَّمَا عِلۡمُهَا عِندَ رَبِّيۖ لَا يُجَلِّيهَا لِوَقۡتِهَآ إِلَّا هُوَۚ ثَقُلَتۡ فِي ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِۚ لَا تَأۡتِيكُمۡ إِلَّا بَغۡتَةٗۗ يَسۡـَٔلُونَكَ كَأَنَّكَ حَفِيٌّ عَنۡهَاۖ قُلۡ إِنَّمَا عِلۡمُهَا عِندَ ٱللَّهِ وَلَٰكِنَّ أَكۡثَرَ ٱلنَّاسِ لَا يَعۡلَمُونَ ١٨٧﴾ الأعراف: ١٨٧

***‹‹ሰአቲቱ መቼ እንደምትረጋ (እንደምትመጣ) ይጠይቁሀል:: እውቀቱዋ በጌታዬ ዘንድ ነው፤ በጊዜዋ እርሱ እንጂ ሌላ አይገልጣትም፤ በሰማያትና በምድር ከበደች፤ 'በድንገት ቢሆን እንጂ አትመጣችሁም' በላቸው፤ ከርሱዋ አጥብቀህ እንደተረዳህ አድርገው ይጠይቁሃል:: 'እውቀቱዋ አላህ ዘንድ ብቻ ነው፤ ግን አብዛኛወቹ ሰዎች አያውቁም' በላቸው::›› (አእራፍ፣ 187)***

﴿يَسۡـَٔلُونَكَ عَنِ ٱلسَّاعَةِ أَيَّانَ مُرۡسَىٰهَا ٤٢ فِيمَ أَنتَ مِن ذِكۡرَىٰهَآ ٤٣ إِلَىٰ رَبِّكَ مُنتَهَىٰهَآ ٤٤ إِنَّمَآ أَنتَ مُنذِرُ مَن يَخۡشَىٰهَا ٤٥ كَأَنَّهُمۡ يَوۡمَ يَرَوۡنَهَا لَمۡ يَلۡبَثُوٓاْ إِلَّا عَشِيَّةً أَوۡ ضُحَىٰهَا ٤٦﴾ النازعات: ٤٢ ـ ٤٦

***‹‹ሰአቲቱ መቼ ነው መሆኛዋ ሲሉ ይጠይቁሃል። አንተ እርሱዋን ከማስታወስ በምን ውስጥ ነህ?። (የእውቀት) መጨረሻዋ ወደ ጌታህ ብቻ ነው። አንተ የሚፈራትን ሰው አስፈራሪ ብቻ ነህ። እነርሱ በሚያዩዋት ቀን ያንዲት ቀን ምሽትን ወይም ረፋዱዋን እንጂ ያልቆዩ ይመስላሉ።››*** *(ናዚኣት፣ 42-46)*

﴿إِنَّ ٱللَّهَ عِندَهُۥ عِلۡمُ ٱلسَّاعَةِ وَيُنَزِّلُ ٱلۡغَيۡثَ وَيَعۡلَمُ مَا فِي ٱلۡأَرۡحَامِۖ وَمَا تَدۡرِي نَفۡسٞ مَّاذَا تَكۡسِبُ غَدٗاۖ وَمَا تَدۡرِي نَفۡسُۢ بِأَيِّ أَرۡضٖ تَمُوتُۚ إِنَّ ٱللَّهَ عَلِيمٌ خَبِيرُۢ ٣٤﴾ لقمان: ٣٤

***‹‹አላህ፣ የሰአቲቱ እውቀት እርሱ ዘንድ ብቻ ነው፣ ዝናብን ያወርዳል፣በማህጸኖችም ውስጥ ያለን ሁሉ ያውቃል፣ ማንኛይቱም ነፍስ በየትኛው ምድር እንደምትሞት አታውቅም፣ አላህ አዋቂ ውስጠ አዋቂ ነው።››*** *(ሉቅማን፣ 34)*

ሰዓቷን የሚመለከት እውቀት በአላህ ብቻ የተገደበ ነው። አንዳንድ ምሁር ነን ባዮችና ተፈላሳፊ ሰዎች የሂሳብ ቀመር እየሰሩ «ትንሳኤ ይህን ያህል ጊዜ ቀረው» እያሉ ህዝብን ለማጭበርበር የሚሞክሩ ቢሆንም፣ ይህ መላምታቸው ከማጭበርበር የዘለለ ነገር አይደለም። በፈረንጆች አቆጣጠር 2000 አመት ሲሞላ «የአለም ፍፃሜ ይሆናል» ሲባልና መገናኛ ብዙሀንን ሲያጨናንቅ የነበረው ጩኸት ለዚህ አብነት ነው። የዚህ አይነቱ ተግባር ቅንጣት ዝንፍ በማይለው የአላህ ቃል ላይ የሚፈፀም ልክ የለሽ ቅጥፈት ነው። ማንም ሰው «ትንሳኤ የሚከሰተው በዚህ ጊዜ ወይም አመት ነው» ማለት አይችልም። ይህን አይነቱ ግምት ልክ የለሽ ቅጥፈት ነው። ነብዩﷺ ለጅብሪል የሰጡት መልስም «***ተጠያቂው ከጠያቂው የበለጠ እውቀት የለውም***» የሚል ነው። ጥበቡ ያለው ስለቂያማ ሰዓት መቼ እንደሚከሰት መጠየቁ ላይ ሳይሆን፣ ለዚያ ቀን ምን ልስራ ከማለትና ራስን ከማዘጋጀት ላይ ነው።

# አምስተኛው የጅብሪል ጥያቄ

## «... ስለምልክቶቿ ይንገሩኝ?»

የመጨረሻው የጅብሪል ጥያቄ «... **ስለምልክቶቿ ይንገሩኝ**?» የሚል ነው:: ቂያማ መቅረቡን የሚያመላክቱ የተለያዩ ምልክቶች አሉ:: አላህﷻ እንዲህ ይላል፡-

﴿ فَهَلْ يَنظُرُونَ إِلَّا ٱلسَّاعَةَ أَن تَأْتِيَهُم بَغْتَةً فَقَدْ جَآءَ أَشْرَاطُهَا فَأَنَّىٰ لَهُمْ إِذَا جَآءَتْهُمْ ذِكْرَىٰهُمْ ﴿١٨﴾ ﴾ محمد: ١٨

***«ሰአቲቱንም ድንገት የምትመጣባቸው መሆኑዋን እንጂ ይጠባበቃሉን? ምልክቶቹዋም በርግጥ መጥተዋል፤ በመጣቻቸውም ጊዜ ማስታወሳቸው ለነርሱ እንዴት ይጠቅማቸዋል::»*** *(ሙሀመድ፣ 18)*

የቂያማ ምልክቶች በጣም በርካታ ናቸው:: የምልክቶቹ አይነት ትልቅ፣ መካከለኛና ትንሽ ተብሎ ይከፈላል:: ከመካከለኛና ከትንንሽ ምልክቶች ውስጥ አብዛኛዎቹ ተከስተው አልፈዋል፤ በመከሰትም ላይ ይገኛሉ:: ታላላቅ ምልክቶች ግን ገና አልተከሰቱም:: በዚህ ዙርያ ብዙ ኪታቦች ስላሉ እነሱን መመልከቱ የተሻለ ይሆናል::

ነብዩﷺ ሁለት ምልክቶችን ነበር፣ ለጅብሪል የጠቀሱለት:: አንደኛው ‹‹**ሴት ባሪያ ጌታዋን ስትወልድ**›› የሚል ነው:: ኡለሞች እንደሚገልፁት ትንሳኤ ሲቃረብ ልጆች ወላጆቻቸውን ይበድላሉ፤ በደሉንም እንደ ተገቢና ተራ ነገር ይቆጥሩታል:: እናም እናት በልጇ ትበደላለች፣ ትንገላታለችም::

ሁለተኛው የቂያማ ምልክት የሚከተለው ነው፤ «**ጫማ የለሽ፣ ድሃ፣ የተራቆቱና ፍየል ጠባቂ የነበሩ ሰዎች በህንፃ ግንባታ ሲፎካከሩ ስታይ::**» በዚህ የቂያማ ምልክት ውስጥ የተገለፁት የገጠር ሰዎች ናቸው:: ድሀ ናቸውና ልብስ በወጉ አይለብሱም፤ ጫማም አይጫሙም:: የስራ ዘርፋቸውም ባብዛኛው ፍየል ጥበቃ ነው:: አስገራሚው ነገር ታዲያ ቂያማ በሚቃረብበት ጊዜ በሰማይ ጠቀስ ህንጻዎች ሲፎካከሩ መታየታቸው ነው:: በዘመናችን ገጠሬ የሆኑ አረቦች አንዱ ከአንዱ የተሻለ ህንጻ ለመስራት ከፍተኛ

ገንዘብ እያፈሰሱ፣ ትልልቅ ህንፃዎችን ለመገንባት ደፋ-ቀና ሲሉ መታየታቸው፣ የትንሳኤ ምልክቶችን አስመልክቶ የነብዩﷺ ንግግር እውነተኛ ለመሆኑ ህያው ምስክር ነው።

## ተፈፀመ

*«ሶሀቦች… ስለዲናቸው ነብዩን ﷺ እየጠየቁ ባለበት ሁኔታ…. ወዘ ልውጥ ሰው ብቅ አለ። ይህ ሰው ለሶሀቦቹ ትእንግርት ሆነባቸው… እንግዳ ነው እንዳይሉ፣ አንድም መንገደኛ መሆኑን የሚጠቁም ምልክት አይታይበትም፤ ልብሱ አላደፈም፤ ይልቁንም በጣም ነጭ ነው። ስንቅ አልያዘም፤ የመጓጓዢያ እንስሳም የለውም…»*

*«….ከመካከላቸው ሙስሊም፣ ከዚያም ሙእሚን፣ ከዚያም ሙህሲን አለ። አንድ ሰው ሙስሊም ሳይሆን ሙዕሚን፣ ሙዕሚን ሳይሆን ሙህሲን ሊሆን አይችልም። እነዚህ ደረጃዎች አንዱ በአንዱ ላይ የተነባበሩና አንዱ ሌላውን ተከትሎ ሊመጣ የሚችል እንዲሁም ስፋትና ጥልቀት ያለው ነው።»*

(*ከመፅሀፉ የተወሰደ*)






إعداد

د/ عادل بن محمد

ترجمة

يوسف محمد

[illegible] 10 [illegible]